ይህንን አስመልክቶ ፒተር ጎሜስ [Peter Gomes] የተባለ አንድ የሐርቫርድ አገልጋይ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከዕለታት በአንድ ቀን ነገረ ማርያምን በሚገባ ያልጠነቀቀ አንድ የፕሮቴስታንት የሥነ መለኮ ት ምሁርን ባገኘው ጊዜ የተናገረውን ኃይለ ቃል እንዲህ ሲል ገልጾታል:- « ፕሮፌሰር! መቼም የባሕርይ አባቴን እንደምታምነው አውቃለሁ፤ ነገር ግን እናቴን ታውቃታለህ ብዬ አልልም» ["Ah, Professor, I know you have met my Father, but I don't believe you know my Mother."][(415)]

## 5.1.22 የወላዲተ አምላክ ዜና ዕረፍት ወፍልሰት (ዕርገት)

በኦርቶዶክሳውያን አብያተ ክርስቲያናት ትውፊት መሠረት ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም በዚህ የእንግድነት ዓለም (1ኛ ጴጥ. 1÷17) በሕይወተ ሥጋ ስልሳ አራት ዓመታት ያህል ቆይታ በክብር አርፋለች:: ቅዱሳን ሐዋርያትም በፈቃደ እግዚአብሔር ከያሉበት መጥተው በኢየሩሳሌም ተሰብስበው የፈጣሪያቸውን እናት ድንግል ማርያምን በጸሎትና በማዕጠንት አክብረው ገንዘው ጥልቅ በሆነ ኃዘን በጌቴሴማኒ ቀብረዋታል::[(416)]

(415) Beima, "Hail Mary," 52.

(416) *መጽሐፈ ፍልሰታ ["The Book of the Assumption of St. Mary"]*, ed. Marius Chaine, *CSCO,* vol. 7, *Scriptores Aethiopici,* 24-31, 41. Heldman, *The Marian Icons of the Painter Fre Seyon: A Study of Fifteenth Century Ethiopian Art, Patronage and Spirituality,* 176. ተሾመ ዘሪሁን (መልአከ ታቦር)፣ *ሰአሊ ለነ ቅድስት፣* ገጽ 20-24፣ 41:: አያሌው ታምሩ (ሊቀ ጠበብት)፣ *ምልጃ፣ ዕርቅና ሰላም፣* ገጽ 60:: *ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፣* ገጽ 207-209:: St. Jacob of Serug, *On the Mother of God,* 94, 98-99. Graef, *The Devotion to our Lady,* 33-34.

ስለ እመቤታችን ቅድስት ድንግል ማርያም ዕረፍትና ዕርገት ሰፋ ያለ ግንዛቤ ለማግኘ ት የሚከተሉትን መጻሕፍት መመልከት በእጅጉ ይጠቅማል:: Stephen J. Shoemaker, *Ancient Traditions of the Virgin Mary's Dormition and Assumption* (New York: Oxford University Press, 2002), 2-77. የወላዲተ አምላክን በዓለ ዕረፍትና ዕርገት አስመልክቶ ስለ ጥንታዊው የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ትውፊት ሰፋ ያለ ግንዛቤ ለማግኘት በዚሁ መጽሐፍ ውስጥ ከገጽ 290-350 ድረስ ያለውን ይመልከቱ:: Brain E. Daley, trans., *On the Dormition of Mary: Early Patristic Homilies* (Crestwood, New York: St. Vladimir's Seminary Press, 1996).





ሥዕል 15:- ዕረፍታ ለእግዝእትነ ማርያም (የእመቤታችን ዕረፍት)

«ሰላም ለጸአተ ነፍስኪ እንበለ ጻዕር ወሕማም፤ ለነቢር ዘልፈ በየማነ ወልድኪ ፌማ»

(«መልክዐ ማርያም» ገጽ 532)

«ሞትሰ ለመዋቲ ይደሉ፣ ሞታ ለማርያም የዓጽብ ለኩሉ፤ ለሟች ሰው ሞት ይገባል:: የእመቤታችን ሞት ግን ሳሁሉ ያስደንቃል::»

(መጽሐፈ ዚቅ ወመዝሙር፣ ገጽ 129)

ይሁን እንጂ በክፍል 5.1.3 ላይ እንደተመለከትነው ቅዱሳን ሐዋርያት እመቤታችንን በክብር ለመሸኘት በጉዞ ላይ ሳሉ አይሁድ "ንዑ ናውዒ ሥጋሃ በእሳት፤ ኑና ሥጋዋን በእሳት እናቃጥል" ብለው በክፋት ተነሣሡ:: በተለይም ደግሞ በእመቤታችን ላይ በክፋትና በተንኰል ከተነሣሡት ከእኒህ አይሁድ መካከል ታውፋንያ የተባለው አይሁዳዊ አማናዊት ታቦተ እግዚአብሔር የሆነችው የድንግል ማርያም ቅዱስ ሥጋ ያረፈበትን አልጋ ለመያዝ እጁን በድፍረት ዘረጋ:: በዚህን ጊዜ ልዑለ ባሕርይ እግዚአብሔር የአሚናዳብ ልጅ ዖዛ እጁን በታቦተ ጽዮን ላይ በድፍረት በመዘርጋቱ ምክንያት ተቀጥቶ እንደቀጣው ሁሉ (2ኛ ሳሙ. 6÷6፤ 1ኛ ዜና መዋ. 13÷7-10)፤ ታውፋንያም በሰማያዊው መልአክ ሰይፍ እጆቹን ተቀጥቷል:: (ሥዕል 11 ይመልከቱ)

ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም ታላቁ ሐዋርያ ብርሃነ ዓለም ቅዱስ ጳውሎስ "ልሄድ ከክርስቶስ ጋር ልኖር እናፍቃለሁ፤ ከሁሉ ይልቅ እጅግ የሚሻል ነውና" (ፊል. 1÷23) ብሎ እንደተናገረው በልጇ በወዳጇ በኢየሱስ ክርስቶስ ፈቃድ ከሚያልፈው ዓለም ወደማያልፈው ዘለዓለማዊ የክርስቶስ መንግሥት ተሸጋግራለች:: በዚህን ጊዜ እመቤታችን በምድር ካለችው ቤተ ክርስቲያን ጋር የሰማያዊቷ ቤተ ክርስቲያንም አክሊል በመሆኗ የሰማይ ሠራዊት በደስታና በዝማሬ ፍጹም አክብረው ተቀብለዋታል::

የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን በየዓመቱ የምታከብረው ይህ የድንግል ማርያም በዓለ ዕረፍት «ስስተርዕዮ» በመባል ይታወቃል:: በአንጻሩ ደግሞ የሥነ መለኮት ሊቃውንት ይህንን ዐቢይ በዓል ["The Feast of the Falling Asleep / The Dormition of the Blessed Virgin Mary"] ይሉታል:: ከዚህም ጋር ቤተ ክርስቲያናችን በየዓመቱ የምታከብረውን የእመቤታችን በዓለ ዕርገት / «ፍልሰታ» ["The Bodily Assumption of the Holy Mother of God"] በማለት ይገልጹታል::(417)

(417) *መጽሐፈ ዕረፍት ["The Book of the Dormition of St. Mary"]*, ed. Victor Arras, *CSOC*, vol. 342, *Scriptores Aethiopici*, t, 66 (text) 34-72. ቅዱስ ያሬድ፣ *ዝማሬ*



ይህንን ዐቢይ ምሥጢር አስመልክቶ የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ሊቃውንት ነቢየ እግዚአብሔር ቅዱስ ዳዊት "ተንሥእ እግዚኦ ውስተ ዕረፍትከ:: አንተ ወታቦተ መቅደስከ፤ አቤቱ ወደ ዕረፍትህ ተነሥ:: አንተና የመቅደስህ ታቦት" (መዝ. 131÷8)፤ እንዲሁም "ወትቀውም ንግሥት በየማንከ በአልባሰ ወርቅ ዑጽፍት ወኁብርት፤ በወርቅ ልብስ ተጎናጽፋና ተሸፋፍና ንግሥቲቱ በቀኝህ ትቆማለች" (መዝ. 44÷9) ሲል የተናገረው ቃለ ትንቢት በንጽሐ ሥጋ፣ በንጽሐ ነፍስ፣ በንጽሐ ልቡና የጸናች የቅድስት ድንግል እመቤታችንን ዕረፍትና ትንሣኤ እንዲሁም ፍልሰት (ዕርገት) በምሥጢር ከማሳየቱም ሌላ ወላዲተ አምላክ በልጇ በወዳጇ በኢየሱስ ክርስቶስ መንግሥት በክብር መኖሯንም በግልጥ ያስረዳል፣ ያስገነዝባል:: (ራእ. 11÷19)

ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም አማናዊት ታቦተ እግዚአብሔር የመሆኗን ምሥጢር ቀደም ብለን በክፍል 5.1.3 ላይ በስፋት ተመልክተናል:: ይኸውም ሊቁ "ከመ ታቦት ሥርጉት በወርቀ ዓይነ ወተርሴስ በድንግልና ማርያም ሥርጉት ሥጋ ወነፍስ"(418) ሲል እንዳመሰገናት ነው:: ዳግመኛም ወደፊት በክፍል 5.1.23 እንደምናየው ኦርቶዶክሳውያን ሊቃውንት በትርጓሜያቸው ይህንን ቃለ ትንቢት ቅዱስ ዮሐንስ በራእዩ ከገለጣት "ንግሥት ሰማይ፤ የሰማይ ንግሥት" (ራእ. 12÷1) ጋር በምሥጢር በማገናዘብ የእመቤታችንን ሁለንተናዊ ክብርና ልዕልና አምልተውና አስፍተው ገልጸውታል::(419)

*መዋሥዕት*፣ ገጽ 174፣ 379:: Ware, *The Orthodox Church*, 260. Mascall, "The Mother of God," 174-175. 178-179. Palmer, *Mary in the Documents of the Church*, 108-109. Tambasco, *What are they Saying about Mary?*, 68-69. Heldman, *The Marian Icons of the Painter Fre Seyon: A Study in Fifteenth Century Ethiopian Art, Patronage, and Spirituality*, 179. Getachew Haile (Professor), *The Mariology of Emperor Zara Yacob of Ethiopia*, 71-79, 82-83, 120-123. O'Carroll, *Theotokos: A Theological Encyclopedia of the Blessed Virgin Mary*, 49-50.

(418) አባ ጽጌ ድንግል፣ "ማኅሌተ ጽጌ"፣ ገጽ 609::

(419) *መዝሙረ ዳዊት ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 242-243፣ 620:: *መሐረ ትርፌ (ሊቀ ሊቃውንት) መጻሕፍተ ሐዲሳት ሠለስቱ ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 423-430::




**ሥዕል 16:- እመቤታችን በክብር እንዳረገች**

"ሰላም ለፍልሰተ ሥጋኪ ደባትሪ ብርሃን ኀበ ተተክሉ፤
ለገነተ ጽባሕ በማዕከሉ፤
ውድስት አንቲ ወስብሕት በአፈ ኩሉ፤
እምነ ጻድቃን ዘታሕቱ ወእምትጉሃን ዘላዕሉ፤
ማርያም ለኪ ስብሐተ ኢደሉ::
("መልክዐ ማርያም"፣ ገጽ 534)



በዚህ ታላቅና ድንቅ ራእይ አማካይነት በተገለጠው አማናዊ ምሥጢር መሠረት ኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያናችን የወላዲተ አምላክ የድንግል ማርያም ትንሣኤና ፍልሰት ከትንሣኤ ዘጉባኤ በኋላ በሚመጣው ዓለም የምንኖረውን ዘላለማዊ ሕይወት አመልካች መሆኑን በሚገባ ታምናለች፣ ታሳምናለች::[420] ይኸውም ሐዋርያው ቅዱስ ዮሐንስ በራእዩ "... በጌታ የሚሞቱ ሙታን ብፁዓን ናቸው:: ... ከድካማቸው ያርፉ ዘንድ ሥራቸውም ይከተላቸዋል" (ራእ. 14÷13) ብሎ እንደመሰከረው እመቤታችን ከዕረፍቷና ዕርገቷ በኋላ የመጨረሻ ወደ ሆነው ፍጹም አምላካዊ ጸጋና ክብር መሸጋገሯን ልብ ይሏል::

ይህንን ቃለ መጽሐፍ ምስክር በማድረግ በኦርቶዶክሳውያን ዘንድ ዘወትር የሚዘመረው የድንግል ማርያም ምስጋና "ወበእንተዝ ናዐብየኪ ኲልነ ኦ እግዝእትነ ወላዲተ አምላክ ንጽሕት ኲሎ ጊዜ:: ንስእል ወናንቅዐዱ ኀቤኪ ከመ ንርከብ ሣህለ በኀበ መፍቀሬ ሰብእ፤ ሁልጊዜ ንጽሕት የምትሆኚ አምላክን የወለድሽ እመቤታችን ሆይ ስለዚህ ነገር እናከብርሻለን፣ እናገንሻለን:: ሰውን ከሚወድ ልጅሽ ዘንድ ይቅርታንና ምሕረትን እናገኝ ዘንድ ሁልጊዜ ዓይነ ልቡናችንን ወደ አንቺ እናነሣለን::"[421] በማለት ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም ከልዑል እግዚአብሔር ዘንድ የተሰጣትን ልዩ የቃል ኪዳን ጸጋና አምላካዊ ክብር በግልጥ ይመሰክራል:: ሊቁ "ቅስተ ደመና ማርያም ትእምርተ ኪዳኑ ለኖኅ፣ ዘእግዚአብሔር ሜመኪ ለተዝካረ ምሕረት ወፍትሕ፣ ህየንተ ቀስፋ ለምድር ወአማስና አይኅ::"[422] ብሎ እንዳመሰገናት::

ኢትዮጵያውያን መተርጉማን ቀደም ብለን የጠቀስነውንና "በወርቅ ልብስ ተጐናጽፋና ተሸፋፍና ንግሥቲቱ በቀኝህ ትቆማለች" (መዝ. 44÷9) የሚለውን የቅዱስ ዳዊትን ቃለ ትንቢት አብነት በማድረግ

[420] Aymro Wondemagegnehu and Motovu, *The Ethiopian Orthodox Church*, 107-108. Graef, *Mary: A History of Doctrine and Devotion*. vol. 1, 50. Bauer, *The Essential Mary Handbook: A Summary of Beliefs, Devotions, and Prayers*, 60.

[421] ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 190::

[422] አባ ጽጌ ድንግል፣ "ማኅሌተ ጽጌ"፣ ገጽ 595-596::

ንግሥተ ሰማይ ወምድር ድንግል ማርያም በንጽሐ ሥጋ፣ በንጽሐ ነፍስ፣ በንጽሐ ልቡና ተሸልማና አጊጣ በሰማያዊው ዓለም በልጇ መንግሥት በክብር መኖሯን አስረግጠው አስረድተዋል:: በዚህም ምክንያት ኦርቶዶክሳውያን ክርስቲያኖች ሰማያዊው አባታቸው እግዚአብሔርን «አቡነ ዘበሰማያት» እያሉ ዘወትር ሲያመሰግኑ፤ በአንጻሩ ደግሞ መንፈሳዊት እናታቸው ድንግል ማርያምን «በሰላመ ቅዱስ ገብርኤል መልአክ ኦ እግዝእትየ ማርያም ሰላም ለኪ» እያሉ ዘወትር ያከብሯታል፣ ያመሰግኗታል::

የነገረ ማርያም ሲቃውንት በስፋት እንደገለጹት ሐዋርያዊት ቤተ ክርስቲያን የምትገለገልበትና «በሰላመ ገብርኤል» የተሰኘው ልዩ የምስጋና ጸሎት በየዘመናቱ የተነሡ አያሌ የቤተ ክርስቲያን ሊቃውንት በወንጌለ ሉቃስ መጀመሪያ ምዕራፍ ላይ የተጻፈውን ገጸ ንባብ ምሥጢሩን በትርጓሜ አስማምተው በማገናዘብ አሁን ያለበትን ደረጃ እንዲይዝ አድርገዋል:: ስለሆነም ሐዋርያዊት ቤተ ክርስቲያን በዚህ የምስጋና ጸሎት አማካይነት ከሰማያዊው ዓለም ጋር ያላትን ምሥጢራዊ ኅብረትና አንድነት ዘወትር ትመሰክርበታለች:: ምክንያቱም ቀደም ብለን እንደተመለከትነው የእመቤታችን የድንግል ማርያም ትንሣኤና ዕርገት ከሞት በኋላ ላለው ሰማያዊ ተስፋና ዘላለማዊ ሕይወት መንገድ ጠራጊና በር ከፋች ነውና::(423)

በኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያናችን ዘወትር የሚጸለየው የድንግል ማርያም ውዳሴ ይህንን ግሩምና ድንቅ የሆነ ታላቅ ጸጋ መሠረት በማድረግ "ለኪ ይደሉ ዘእምኵሎሙ ቅዱሳን ተሰአሊ ለነ ኦ ምልዕተ ጸጋ:: አንቲ ተዐብዪ እምሊቃነ ጳጳሳት:: ወፈድፋደ ትከብሪ እምነቢያት:: ብኪ ግርማ ራእይ ዘየዓቢ እምግርማ ሱራፌል ወኪሩቤል:: አንቲ በአማን ምክሐ ዘመድነ:: ወሰአሊት ሕይወተ ለነፍሳቲነ»(424)፤ ምልዕተ ጸጋ፣ ምልዕተ ክብር፣ ምልዕተ ውዳሴ የሆንሽ ድንግል ሆይ ከቅዱሳን ሁሉ ይልቅ ትለምኝልን ዘንድ

(423) Shoemaker, *Ancient Traditions of the Virgin Mary's Dormition and Assumption*, 375-396. Mascall, "The Mother of God," 178-179. Laurentin, *The Hail Mary: Its Meaning and Its Meaning and Its Origin*, xi.

(424) *ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፣* ገጽ 205::



ላንቺ ይገባል:: አንቺ ከሊቃነ ጳጳሳት ትበልጫለሽ:: ከቅዱሳን ነቢያት፣ ከቅዱሳን ሐዋርያት፣ ከሰብዓ አርድእትም ትበልጫለሽ:: ዳግመኛም ከሱራፌልና ከኪሩቤል ይልቅ የሚበልጥ የመወደድ፣ የመፈራት ግርማ አለሽ:: በእውነት የባሕርያችን መመኪያ ነሽ:: ለሰውነታችንም ሕይወትን፣ ድኅነትን የምትለምኚና የምታማልጅን አንቺ ነሽ በማለት ልዕልናዋን፣ የጸጋዋን ፍጹምነትና የክብሯን ታላቅነት በአጽንኦት ገልጾ መስክሮአል::

## 5.1.23 ንግሥተ ሰማይ (የሰማይ ንግሥት)

ወንጌላዊው ቅዱስ ዮሐንስ ከሦስቱ አካላት አንዱ አካል እግዚአብሔር ወልድ በተለየ አካሉ ከእመቤታችን በተዋሕዶ ሰው ሆኖ በመዋዕለ ሥጋዌው ያደረገውን የድኅነተ ዓለም ጉዞ አምልቶና አስፍቶ የጻፈና የመሰከረም ታላቅ ሐዋርያ ነው:: ይህ ሐዋርያ ምሥጢረ ድኅነት የተፈጸመበትን አምላካዊ የቸርነት ሥራ በተናገረበት አንቀጽ ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያምን ከነገረ ድኅነት ጋር በተያያዘ መልኩ ያላትን መሠረታዊ ሱታፌና ከፍተኛ ሚና በግልጽ መስክሮአል:: ለምሳሌ ያህል መድኅነ ዓለም ኢየሱስ ክርስቶስ የመጀመሪያውን አምላካዊ ድንቅ ተአምር ባደረገበት በቃና ዘገሊላ ሠርግ ቤት እመቤታችን ከልጇ ከወዳጇ ጋር እንደነበረችና ለተአምሩም ምክንያት እንደሆነች ተመልክተናል:: (ዮሐ. 2÷1-11)

ከላይ እንደገለጥነው በገሊላ ቃና የተፈጸመው ታላቅና ድንቅ አምላካዊ የቸርነት ሥራ ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በዕለተ ዓርብ የፈጸመውን የቤዛነት ሥራ በምሥጢር ያጠይቃል:: ይህም ይታወቅ ዘንድ ወሀቤ ሕይወት የሆነው ጌታ ለድኅነተ ዓለም ሲል በቀራንዮ አደባባይ በተሰቀለባትና ማየ ሕይወት የሆነውን አማናዊ ወይን ደሙን ባፈሰሰባት ዕለት ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም ከእግረ መስቀሉ አጠገብ ነበረች:: በዚህም አዲሲቷ ሔዋን እመቤታችን በክርስቶስ ቤዛነት ለዳነውና በወርቀ ደሙም ለተዋጀው አዲሱ የሰው ዘር ማለትም

የክርስቶስ ምሥጢራዊ አካል (ቤተ ክርስቲያን) መንፈሳዊት እናት ሆና በጸጋ ተሰጥታናለች:: (ዮሐ. 19÷26-27)

ሌላው ምሥጢር ደግሞ አቡቀለምሲስ (ራእየ ኅቡዓት፤ ባለ ራእይ) የተባለው ቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊ በራእዩ የሰማያዊው ንጉሥ ክርስቶስ እናት በመሆኗ ንግሥተ ሰማይ ስለተባለችው ስለ ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም ክብርና ልዕልና በሰፊው ተናግሮአል:: ሐዋርያው ታላቅና ድንቅ በሆነው በዚህ ምሥጢራዊ ራእዩ ሲናገር:-

> *ታላቅ ምልክትም በሰማይ ታየ፤ ፀሐይን ተጐናጽፋ ጨረቃ ከእግሮችዋ በታች ያላት፤ በራስዋም ላይ የአሥራ ሁለት ከዋክብት አክሊል የሆነላት አንዲት ሴት ነበረች:: እርስዋም ፀንሳ ነበር÷ ምጥም ተይዛ ልትወልድ ተጨንቃ ጮኸች:: ... ዘንዶውም ሴቲቱ በወለደች ጊዜ ሕፃንዋን እንዲበላ ልትወልድ ባላት ሴት ፊት ቆመ:: አሕዛብንም ሁሉ በብረት በትር ይገዛቸው ዘንድ ያለውን ወንድ ልጅ ወለደች፤ ልጅዋም ወደ እግዚአብሔርና ወደ ዙፋኑ ተነጠቀ:: ሴቲቱም ሺህ ከሁለት መቶ ስልሳ ቀን በዚያ እንዲመግቡአት በእግዚአብሔር ተዘጋጅቶላት ወደ ነበረው ስፍራ ወደ በረሀ ሸሸች (ራእ. 12÷1-6)*

> *"... ዘንዶውም ወደ ምድር እንደተጣለ ባየ ጊዜ ወንድ ልጅ የወለደችውን ሴት አሳደዳት:: ከእባቡም ፊት ርቃ አንድ ዘመን÷ ዘመናትም÷ የዘመን እኩሌታ ወደምትመገብበት ወደ ስፍራዋ፣ ወደ በረሀ እንድትበር ለሴቲቱ ሁለት የታላቁ ንሥር ክንፎች ተሰጣት:: እባቡም ሴቲቱ በወንዝ እንድትወሰድ ሊያደርግ ወንዝ የሚያህልን ውኃ ከአፉ በስተ ኋላዋ አፈሰሰ:: ምድሪቱም ሴቲቱን ረዳቻት÷ ምድሪቱም አፍዋን ከፍታ ዘንዶው ከአፉ ያፈሰሰውን ወንዝ ዋጠችው:: ዘንዶውም በሴቲቱ ላይ ተቈጥቶ የእግዚአብሔርን ትእዛዛት የሚጠብቁትን የኢየሱስም ምስክር ያላቸውን ከዘርዋ የቀሩትን ሊዋጋ ሄደ፤ በባሕርም አሸዋ ላይ ቆመ::" (ራእ. 12÷13-17)* ሲል መስክሮአል::



በዚህ ታላቅና ድንቅ ራእይ መሠረት ፀሐይን የተጐናጸፈች፣ ጨረቃ ከእግሮቿ በታች ያላትና የአሥራ ሁለት ከዋክብት አክሊል የተቀዳጀች ሴት የተባለችው ቅድስት ድንግል ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም ናት:: ስለሆነም ፀሐይን ተጐናጽፋለች ማለት ምሥጢራዊ ትርጓሜው እመቤታችን ፀሐየ ጽድቅ (ሚል. 4÷2፤ ማቴ. 17÷2) ኢየሱስ ክርስቶስን ወልዳለች ማለት ነው:: ሊቁም "... ፀሐየ ጽድቅ ሰርቀ ለኪ ዘበአማን ውእቱ ኢየሱስ ክርስቶስ" በማለት አጽንቶታል:: ከዚህም ጋር ከእግሮቿ በታች ጨረቃ መታየቱ ቅዱስ ዮሐንስ መጥምቅ በእናቱ ማኅፀን ሳለ ለፈጣሪው እናት ለድንግል ማርያም በጸጋ መስገዱን በምሥጢር ያስተረጉማል::(425) (ሉቃ. 1÷41)

የቤተ ክርስቲያናችን መተርጉማን ቅዱስ ዮሐንስ መጥምቅ በጨረቃ የተመሰለበትን ምሥጢር ሲያብራሩ ጨረቃ ሠርቅ ካደረገች በኋላ ማለትም ከወጣችበትና መታየት ከጀመረችበት እስከ አሥራ አምስት ቀናት ድረስ ምልዓት እያሳየች ትቆያለች:: ከአሥራ አምስት ቀን በኋላ ግን ሕጸጽ (ጉድለት) እያመጣች ትሔዳለች:: እንደዚሁም ሁሉ ጸያሔ ፍኖት ቅዱስ ዮሐንስ መጥምቅ ለአሥራ አምስት ዓመታት ያህል ወልደ እግዚአብሔር እንደነገሠ፣ ዲያብሎስ እንደተሻረ፣ መርገመ ሥጋ፣ መርገመ ነፍስ እንደቀረ፣ ድኅነተ ሥጋ፣ ድኅነተ ነፍስ እንደተገኘ የምትናገር የምሥራች ወንጌልን ዞሮ ካስተማረ በኋላ በሰማዕትነት በክብር አርፏልና በጨረቃ ከመመሰሉ ምሥጢር ጋር ይስማማል::(426)

ይህንን አስመልክቶ ሊቁ ቅዱስ ያዕቆብ ዘሥሩግ በነገረ ማርያም የምሥጢር መድበሉ ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም

(425) አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ፣ *መጽሐፈ ሰዓታት*፣ ገጽ 158:: *መሐሪ ትርፌ* (ሊቀ ሊቃውንት) *መጻሕፍተ ሐዲሳት ሠለስቱ ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 425::

(426) *መሐሪ ትርፌ* (ሊቀ ሊቃውንት) *መጻሕፍተ ሐዲሳት ሠለስቱ ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 425::

ቅድስት ኤልሳቤጥን በጐበኘችት ጊዜ የተገለጠውን ድንቅ ምሥጢር በማነጻጸር ሲመሰክር «ንጋትና ምሽት ወይም ደግሞ መዓልትና ሌሊት ተገናኙ»[427] በማለት አድንቋል። በዚህ ኃይለ ቃል መሠረት በንጋት ወይም በመዓልት የተመሰለችው የፀሐየ ጽድቅ የኢየሱስ ክርስቶስ እናት የሆነችው እመ ብርሃን ቅድስት ድንግል እመቤታችን ናት። በአንጻሩ ደግሞ በምሽት ወይም ደግሞ በሌሊት የተመሰለችው የብርሃነ ወርኅ (የጨረቃ ብርሃን) የቅዱስ ዮሐንስ መጥምቅ እናት ቅድስት ኤልሳቤጥ ናት። ወንጌላዊው ቅዱስ ዮሐንስም «ወአንትሙ ፈቀድክሙ ትትፌሥሑ በብርሃኑ እስከ ሰዓት። ወዝንቱ ውእቱ ማኅቶት ዘየሐቱ ወያበርህ፤ የሚነድና የሚያበራ ፋና ይህ ዮሐንስ ነው። እናንተ በትምህርቱ መንፈቅ ደስ ሊላችሁ ወደዳችሁ» (ዮሐ. 5÷35) ሲል የመጥምቀ መለኮት ቅዱስ ዮሐንስን ትምህርት በፋና፣ የጌታን ትምህርት ደግሞ በፀሐይ መስሎ ተናግሮአል።[428]

ሊቀ ነቢያት ሙሴ የሥነ ፍጥረትን የት መጣና ህልውና በተናገረበት አንቀጽ «እግዚአብሔርም አለ፦ ቀንና ሌሊትን ይለዩ ዘንድ ብርሃናት በሰማይ ጠፈር ይሁኑ ... እግዚአብሔርም ሁለት ታላላቆች ብርሃናትን አደገ፤ ትልቁ ብርሃን (ፀሐይ) በቀን እንዲሰለጥን ትንሹም ብርሃን (ጨረቃ) በሌሊት እንዲሰለጥን ... አደረገ» (ዘፍ. 1÷14-19) ሲል ገልጿል። በዚህ መሠረት ፀሐይ ብርሃነ መዓልት ሲሆን ጨረቃ ደግሞ ብርሃነ ሌሊት ነው። ከዚህም ፀሐየ ጽድቅ የሆነ ጌታ የተገኘባት እመቤታችን በንጋት ወይም በመዓልት የተመሰለችበትን፤ እንዲሁም የመጥምቀ መለኮት ቅዱስ ዮሐንስ እናት ቅድስት ኤልሳቤጥ ደግሞ በምሽት ወይም በሌሊት የተመሰለችበትን ምሥጢር ልብ ይሏል።

ሐዋርያው ቅዱስ ዮሐንስ ፀሐይን ተጐናጽፋና ጨረቃ ከእግሮቿ በታች ባላት ሴት ራስ ላይ እንደ ዕንቁ ፈርጥ ሲያበሩ ያያቸው አሥራ ሁለቱ ብሩሃን ከዋክብት የአሥራ ሁለቱ ቅዱሳን

(427) St. Jacob of Serug, *On the Mother of God*, 49.
(428) *ወንጌል ቅዱስ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 481።*



ሐዋርያት ምሳሌዎች ናቸው። በቅዱሳት መጻሕፍት ትርጓሜ ምሥጢር መሠረት ሰዎችን አስተምረውና መክረው ከአምልኮተ ጣዖት ወደ አምልኮተ እግዚአብሔር፣ ከሰይጣን ወደ ክርስቶስ፣ ከኦሪት ወደ ወንጌል፣ ከገቢረ ኃጢአት ወደ ገቢረ ጽድቅ፣ ከክፋት ወደ በጎነት፣ ከባርነት ወደ ልጅነት፣ ከኃጢአት ወደ ሥርየት፣ ከሲኦል ወደ ገነት መልሰው ከልዑለ ባሕርይ እግዚአብሔር ጋር በንስሐ የሚያገናኙና የሚያስታርቁ መምህራን በከዋክብት ይመሰላሉ። (ማቴ. 5÷9፣ 14-16)

ይህንን አስመልክቶ ነቢየ እግዚአብሔር ዳንኤል ሲናገር «ወእለሰ ይጠይቁ ብዙኃነ ሰብአ ኀበ ጽድቅ ወያበርሁ ከመ ከዋክብተ ሰማይ ለዓለመ ዓለም፤ ብዙዎችን አስተምረውና መክረው ከአምልኮተ ጣዖት ወደ አምልኮተ እግዚአብሔር፣ ከገቢረ ኃጢአት ወደ ገቢረ ጽድቅ፣ ከክፋት ወደ በጎነት፣ ከኃጢአት ወደ ሥርየት በንስሐ የሚመልሱና ባሕረ ምሕረት ወደብረ ትዕግሥት ከሆነው ቸሩ አምላክ ጋር የሚያገናኙ መምህራን እንደ ሰማይ ከዋክብት ለዘላለም ያበራሉ፣ ይደምቃሉ» (ዳን. 12÷3) በማለት መስክሮአል።

ከዚህም ጋር በዜና አበው ክፍለ ትምህርት እንደምንረዳው በአራተኛው መቶ ክፍለ ዘመን ከነበሩት ሦስቱ የቀጳዶቅያ አባቶች [The Three Cappadocian Fathers] ማለትም ከቅዱስ ባስልዮስ ዘቂሣርያ፣ ቅዱስ ጎርጎርዮስ ዘኑሲስና ቅዱስ ጎርጎርዮስ ዘእንዚናዙ መካከል አንዱ የሆነው ሊቁ ቅዱስ ጎርጎርዮስ ዘኑሲስ እኁሁ ለባስልዮስ (የቅዱስ ባስልዮስ ወንድም) «የኑሲስ ኮከብ» ["The Star of Nyssa"] በመባል ይታወቃል። ይህም ሊሆን የቻለበት ዋነኛው ምክንያት ይህ ታላቅ አባት በተሰጠው ጸጋ እግዚአብሔርና አምላካዊ አደራ መሠረት በጣዕመ ስብከቱ፣ በአባታዊ ምክሩ፣ ዘወትር በሚያዘጋጃቸው ትምህርታዊ ጽሑፎቹና በሁለንተናዊ ሕይወቱም መልካም አርአያ በመሆን የኑሲስ ምእመናንን በትምህርተ ሃይማኖት አንጾ፣ በክርስቲያናዊ ሥነ ምግባር ቀርጾ፣ በንስሐ ከእግዚአብሔር ጋር ስላገናኛቸውና ስላስታረቃቸው ነው። ስለሆነም

የኑሲስ ክርስቲያኖች በጨለማ ኃጢአትና ድንቁርና ተውጦ የነበረውን ሁለንተናዊ ሕይወታቸውን በወንጌል ብርሃን ያበራላቸው ቅዱስ ጎርጎርዮስን «አባታችን በእውነት የኑሲስ ኮከብ ልትባል ይገባሃል» ያሉት በጌታችን ዕለተ ልደት ሰብአ ሰገልን (የጥበብ ሰዎችን) አምልኮተ ጣዖት ከሰፈነበትና ገቢረ ኃጢአት ከበዛበት ከሩቅ ምሥራቅ እየመራ እውነተኛው አምላክ ከእመቤታችን ተወልዶ በፍጹም ትሕትና ወደ ተገለጠባት ኤፍራታ ቤተ ልሔም መርቶ ያመጣቸውንና በፊቱ ያደረሳቸውን ብርሃናዊ ኮከብ አብነት፣ መሠረት አድርገው ነው:: (ማቴ. 2÷1-2፣ 9-11)

ሌላው ምሥጢር ደግሞ ንግሥተ ሰማይ እመቤታችን ቅድስት ድንግል ማርያም በራሷ ላይ የተቀዳጀችው ባለ አሥራ ሁለት ከዋክብት አክሊል በበዓለ ኀምሳ በቅዱሳን ሐዋርያት ላይ ያደረ መንፈስ ቅዱስ ከእናቷ ማኅፀን ጀምሮ የቀደሳትና ያከበራት፣ በመዓዛ ንጽሕና፣ በመዓዛ ቅድስና የሸለማት፣ በድንግልናም ያስጌጣት መሆኑን በምሥጢር ያስረዳል፣ ያስገነዝባል:: ዳግመኛም ይኸው ቅዱስ መንፈስ ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም አካላዊ ቃል እግዚአብሔር ወልድን ያለ ዘርዐ ብእሲ በኅቱም ድንግልና ፀንሳ፣ በኅቱም ድንግልና እንድትወልደው ማድረጉንም ያጠይቃል:: ይህም ቀደም ብለን እንደጠቀስነውና መልአከ ሰላም ቅዱስ ገብርኤል በዕለተ ብሥራት «መንፈስ ቅዱስ በአንቺ ላይ ይመጣል» (ሉቃ. 1÷35) ሲል ስለ ርደተ መንፈስ ቅዱስ (ስለ መንፈስ ቅዱስ መውረድ) የገለጸው ቃለ በረከት ቅዱሳን ሐዋርያት ከትንሣኤ በኋላ በበዓለ ኀምሳ ይቀበሉት ዘንድ ያላቸውን የመንፈስ ቅዱስ ኃይልና ጸጋ ያመለክታል ካልነው ትርጓሜ ጋር በምሥጢር ይገናዘባል:: (የሐዋ. ሥራ 2÷1-21)

በመሆኑም ከላይ በዝርዝር የገለጥነው የእመቤታችን የቅድስት ድንግል ማርያም ክብር በአንድ ዮሐንስ መጥምቅና በቅዱሳን ሐዋርያት ብቻ ተወስኖ የሚቀር ሳይሆን ወደፊትም እስከ ዘላለም ድረስ የማያቋርጥ የምስጋና ምንጭ መሆኑን ልብ ይሏል:: ይህንን አስመልክቶ የቤተ



ክርስቲያናችን የነገረ ማርያም ሊቅ ሲናገር «ኢየዓርብ ፀሐያ ወኢይጸልም ወርኃ ወኢይጠፍኡ ከዋክብቲሃ፤ ፀሐይዋ አይጠልቅም፣ ጨረቃዋም አይጨልምም፣ ከዋክብቶቿም አይጠፉም»(429) በማለት ክብረ ቅድስት ድንግል ማርያም ዘወትር እንደ ፀሐይ ፀዳል በርቶ፣ እንደ ጨረቃ ደምቆ፣ እንደ ከዋክብት አሸብርቆ የሚኖር ሕያው ምሥጢር መሆኑን አስረግጦ መስክሮአል::

ሐዋርያው ቅዱስ ዮሐንስ «ሴቲቱም ፀንሳ ነበር÷ ምጥም ተይዛ ልትወልድ ተጨንቃ ጮኸች» ማለቱ ብእሲት እመቤታችን ወሀቤ ሕይወት ጌታን እንበለ ዘርእ፣ እንበለ ሩካቤ ፀንሳለች ሲል ነው:: ዳግመኛም «... እንደ ታተመ መጽሐፍ ቃል ሆኖባቸዋል» (ኢሳ. 29÷12) ተብሎ በተነገረው ቃለ ትንቢት መሠረት ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም ወልደ እግዚአብሔርን በኅቱም ድንግልና የመፅነሷ ምሥጢር ለአይሁድ ልቡና የረቀቀ፣ ለአእምሮአቸውም የመጠቀ አምላካዊ ምሥጢር በመሆኑ ምክንያት አይሁድ ማየ ዘለፋን እንደሚያጠጧትና በመከራም እንደሚያስጨንቋት ሲያመለክት ነው እንጂ በእመቤታችንስ አካላዊ ቃልን ስትፀንስውም ሆነ ስትወልደው ሕማምና ምጥ፣ ጭንቅና ድካም ፈጽሞ የለባትም::

ይህንን አስመልክቶ ሶርያዊው ሊቅ ቅዱስ ኤፍሬም «እም ኀበ እብ ወጽአ ቃል ዘእንበለ ድካም:: ወእምድንግል ተወልደ ዘእንበለ ሕማም፤ አካላዊ ቃል እግዚአብሔር ወልድ ከባሕርይ አባቱ ከአብ እካለ ዘእምእካለ ባሕርይ ዘእምባሕርይ ድካም ሳይሰማው ተወለደ:: ዳግመኛም አምስት ሺህ አምስት መቶ ዘመን ሲፈጸም ቅድስት ድንግል እመቤታችንን ሕማም ሳይሰማት፣ እርሱንም ሕፃናትን የሚሰማ ሳይሰማው ተወለደ::»(430) በማለት በአጽንኦት ገልጿል:: ይኸውም አስቀድሞ ልዑለ ቃል ኢሳይያስ «ሳታምጥ ወለደች፤ ምጥም ሳያገኛት ወልድን ወለደች:: ከቶ እንዲህ

(429) Getachew Haile (Professor), *The Mariology of Emperor Zara Yacob of Ethiopia*, 78. St. Jacob of Serug, *On the Mother of God*, 28. አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ፣ *መጽሐፈ ሰዓታት*፣ ገጽ 28-29:: ቅዱስ ያሬድ፣ «አንቀጸ ብርሃን»፣ ገጽ 405::

(430) *ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 128::

ያለ ነገር ማን ሰምቶአል? እንዲህስ ያለ ነገር ማን አይቶአል?» (ኢሳ. 66÷7-8) ብሎ የተናገረው ቃለ ትንቢት ይደርስና ይፈጸም ዘንድ ነው:: ከዚህም መዝገበ ቃል የሆነችው ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም «መጽሐፋ ለኢሳይያስ»(431) የተባለችበትን ታላቅና ድንቅ ምሥጢር ያስተውኋል::

ሌላው ደግሞ «ዘንዶውም ሴቲቱ በወለደች ጊዜ ሕፃንዋን እንዲበላ ልትወልድ ባላት ሴት ፊት ቆመ» የሚለው ገጸ ንባብ ምሥጢራዊ ትርጓሜው ቅድስት ድንግል እመቤታችን አሕዛብን ሁሉ በጽኑ ሥልጣኑ የሚገዛውን መድኀነ ዓለም ኢየሱስ ክርስቶስን በወለደች ጊዜ ዘንዶ የተባለ ዲያብሎስ (ራእ. 12÷7-9) በንጉሡ ሄሮድስ ልቡና አድሮ ማኅየዊ (አዳኝ) የሚሆን ኃያል ጌታን ያስገድለው ዘንድ በክፋት ተነሣ ማለት ነው:: ዳግመኛም ሐዋርያው «ልጇም ወደ እግዚአብሔርና ወደ ዙፋኑ ተነጠቀ» ሲል ምሥጢሩ ምንም እንኳን ዳግማዊ አዳም መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ተድላ ደስታ ከሞላባት ከክብር ቦታ ከገነት የተሰደደ ቀዳማዊ አዳምን ወደ ቀደመ ክብሩ፣ ወደ ጥንተ ርስቱ ለመመለስ ሲል ከእመቤታችን በነሣው ሥጋ ቢሰደድም ቅሉ በጌትነቱ ከባሕርይ አባቱ ከአብ፣ ከባሕርይ ሕይወቱ ከመንፈስ ቅዱስ ጋር በዘባነ ኪሩቤል መኖሩን ያስረዳል::(432) ምክንያቱም መጽሐፍ «ኵለንታሁ በአርያም ወኵለንታሁ በከርሠ ማርያም» ብሎ እንደመሰከረው ዋሕድ ቃለ እግዚአብሔር በማኅፀነ ድንግል በተፀነሰ ጊዜ በምልዓት፣ በጌትነት ከአብ ከመንፈስ ቅዱስ ጋር በጽርሐ አርያምም አለና ነው::

ኢትዮጵያዊው ቄርሎስ አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫም «ሶበ ንሔልዮ ከመ እምገሊላዊት ተወልደ፤ ንሔሊ ከመ ተሰዓለ ኀበ አቡሁ:: ሶበ ንሔልዮ ከመ

(431) *ዕዝራ ሐዲስ (ሊቀ ሊቃውንት)፣ መጽሐፈ ትንቢተ ኢሳይያስ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 198-199:: መጻሕፍተ ሐዲሳት ሠለስቱ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 423-425፣ 427::* Getachew Haile (Professor), *The Mariology of Emperor Zara Yacob of Ethiopia*, 71-85. St. Jacob of Serug, *On the Mother of God*, 146-147. Graef, *Mary: A History of Doctrine and Devotion*, 28-30.

(432) *መሐሪ ትርፌ (ሊቀ ሊቃውንት) መጻሕፍተ ሐዲሳት ሠለስቱ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 425::*



በስብሬኪሃ ተሐቅፈ፤ ንሔሊ ከመ ውስተ ሕፅነ አቡሁ ሀሎ::»(433) በማለት አስረግጦ ተናግሮአል::

ከዚህም ጋር ሐዋርያው «ሴቲቱም ሺህ ከሁለት መቶ ስልሳ ቀን በዚያ እንዲመግቡአት በእግዚአብሔር ተዘጋጅቶላት ወደነበረው በረሀ ሸሸች» ማለቱ እመቤታችን ድንግል ማርያም ንጉሡ ሄሮድስ በክፋትና በምቀኝነት ተነሣሥቶ ልጇ ኢየሱስ ክርስቶስን ሊገድልባት በተነሣ ጊዜ ከሄሮድስ ቁጣ ሸሽታ ወደ ምድረ ግብፅ ሄደች፣ በዚያም ሦስት ዓመት ከመንፈቅ ቆየች ማለት ነው:: (ኢሳ. 19÷1-2፤ ሆሴ. 11÷1፤ ማቴ. 2÷13) የቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም ስደት ከነገረ ድኅነት ጋር የተያያዘ ጥልቅ ምሥጢር አለው:: ይኸውም ሊቃውንተ ቤተ ክርስቲያን በትርጓሜ መጻሕፍት እንደገለጹት ዳግሚት ኅትምት ምድር ከተባለች እመቤታችን የተገኘው (የተወለደው) ዳግማዊ አዳም ክርስቶስ ወደ ምድረ ግብፅ መሰደዱ ከቀዳሚት ኅትምት ምድር ለተገኘ ቀዳማዊ አዳም እንደካሣለት ያጠይቃል::(434) (ሥዕል 12 ይመልከቱ)

ዳግመኛም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወደ ምድረ ግብፅ መሰደዱ ለአምስት ሺህ አምስት መቶ ዘመናት በሰው ልጆች ልቡና ዙፋኑን ዘርግቶ፣ በሕይወታቸው ነግሦ ጣዖት ሲያስመልክ፣ ኃጢአት ሲያሠራ ይኖር የነበረው ጥንተ ጠላታችን ዲያብሎስ ከሰው ልቡና ወጥቶ መሰደዱን በምሥጢር ያሳያል:: ትርጓሜ ወንጌል ይህንን አምላካዊ ድንቅ ጥበብና ቸርነት አስመልክቶ ሲናገር «ጉየተ ሕፃን ስጉየዮ ለዲያብሎስ፤ የሕፃን ክርስቶስ መሰደድ ጠላት ዲያብሎስን ከሰው ልጆች ልቡና ተለይቶ ወጥቶ እንዲሰደድ አደረገው»(435) በማለት በአጽንኦት መስክሮአል::

(433) አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ [Abba Giyorgis of Gascha]፣ *መጽሐፈ ምሥጢር* [*"The Book of Mystery"*]፣ ገጽ 236::

(434) *ወንጌል ቅዱስ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 79-80:: መሐሪ ትርፌ (ሊቀ ሊቃውንት) መጻሕፍተ ሐዲሳት ሠለስቱ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 424-425::*

(435) *ወንጌል ቅዱስ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 80::*

ከዚህ በተጨማሪ ደግሞ ጌታችን በአንቀጸ ብፁዓን ስብከቱ "ስለ ጽድቅ የሚሰደዱ ብፁዓን ናቸው፥ መንግሥተ ሰማያት የእነርሱ ናትና" (ማቴ. 5÷10) ብሎ እንዳስተማረው እመቤታችን ድንግል ማርያም ከልጇ፣ ከወዳጇ ከኢየሱስ ክርስቶስ ጋር ወደ ምድረ ግብፅ መሰደዷ የቅዱሳን ሰማዕታትን ስደት ባርኳል:: በዚህም ምክንያት የቤተ ክርስቲያናችን መጻሕፍተ ውዳሴያትና ቅዳሴያት ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያምን "እሞሙ ለሰማዕታት፤ የቅዱሳን ሰማዕታት እናታቸው"፤ "አክሊሎሙ ለሰማዕታት፤ የቅዱሳን ሰማዕታት የድል አክሊላቸው አንቺ ነሽ"(436) እያሉ ዘወትር ያመሰግኗታል፣ ከፍ ከፍ ያደርጓታል::

ሐዋርያው ቅዱስ ዮሐንስ ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም በምድረ ግብፅ በስደት የቆየችባቸውን ጊዜያት በሁለት ዓይነት የቀመር ስልት ገልጾታል:: ይኸውም በመጀመሪያው ቀመር መሠረት "ሴቲቱም ሺህ ከሁለት መቶ ስልሳ ቀን በዚያ እንዲመግቡአት በእግዚአብሔር ተ ዘጋጅቶላት ወደ ነበረው በረሀ ሸሸች" (ራእ. 12÷6) ብሎ እመቤታችን ሦስት ዓመት ከመንፈቅ በምድረ ግብፅ መቆየቷን ይናገራል:: በሁለተኛው ቀመር ደግሞ "ከእባቡም ፊት ርቃ አንድ ዘመን፣ ዘመናትም፣ የዘመን እኩሌታ ወደምትመገብ በት ወደ ስፍራዋ ወደ በረሀ እንድት በር ..." (ራእ. 12÷11) በማለት ከላይ የገለጥነውን የጊዜ ቀመር በሌላ አገላለጽ አስረድቷል:: በዚህም ገጸ ንባብ መሠረት አንድ ዘመን የሚ ለው አንድ ዓመት፣ ዘመናት የሚለው ደግሞ ሁለት ዓመታት፣ እንዲሁም የዘመን እኩሌታ የሚለው ግማሽ ዓመት (መንፈቅ) በድምሩ ሦስት ዓመት ከመንፈቅ ማለት መሆኑን በቀላሉ መረዳትና መገንዘብ ይቻላል::

ሌላው ዐቢይ ምሥጢር ደግሞ "... ለሴቲቱ ሁለት የታላቁ ንሥር ክንፎች ተሰጣት" የሚለው ኃይለ ቃል ንጽሕት በድንግልና፣ ሥርጉት በቅድስና፣ ክብርት በልዕልና የሆነችው እመቤታችን ቅድስት

(436) *ወንጌል ቅዱስ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 80:: ቅዱስ ያሬድ፣ መጽሐፈ ድጓ፣ ገጽ 383-384:: ቅዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 109::*



ድንግል ማርያም ንጽሐ ሥጋና ንጽሐ ነፍስ፤ አንድም ድንግልና ሥጋና ድንግልና ነፍስ እንደተሰጣት ያጠይቃል:: ነቢየ እግዚአብሔር ቅዱስ ዳዊት ይህንን ልዩና ድንቅ ምሥጢር አስመልክቶ ሲናገር "ክነፈ ርግብ በብሩር ዘግቡር ወገበዋቲሃኒ በሐመልማለ ወርቅ:: እመ አዘዘ ሰማያዊ ንጉሥ ላዕሌሃ፤ ሰማያዊው ንጉሥ በእርሷ ላይ አዟልና ክንፎቿ እንደ ርግብ ክንፍ በብር ያጌጡና የተሸለሙ ናቸው:: ጐኖቿም በወርቅ ሐመልማል የተለበጡ ናቸው" (መዝ. 67÷31) ብሏል:: የዚህ ቃለ ትንቢት ትርጓሜ ምሥጢሩም ለማናምቱ ለሳማዊት ርግብ ድንግል ማርያም በንጽሐ ሥጋ፣ በንጽሐ ነፍስ፣ በንጽሐ ልቡና የተሸለመችና ያጌጠች መሆኗን፤ አንድም በድንግልና ሥጋ፣ በድንግልና ነፍስ፣ በድንግልና ኅሊና ኅትምት፣ ጽንዕት፣ ፍጽምት እንደሆነች ያስረዳል:: ዳግመኛም የዋሂት ርግብ እመቤታችን ልቡናዋ "ይኩነኒ በከመ ትቤለኒ፤ እንደ ቃልህ ይሁንልኝ፣ ይደረግልኝ" በሚለው ቃለ ተአምኖ የጸና ምክንያተ ድኅነት መሆኗን ያስገነዝባል::(437) ኢትዮጵያዊው የዜማ ሊቅ ቅዱስ ያሬድ በምስጋና ድርሰቱ "በአምሳለ ያፍ ፀዓዳ ርግብ ትመስሊ ማርያም ድንግል ... እሙ ለአማኑኤል፤ የፈጣሪያችን የአማኑኤል እናቱ ድንግል ማርያም ነጭ ርግብን ትመስላለች"(438) ሲል ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም በንጽሕና፣ በቅድስና፣ በድንግ ልና የጸናች እመ ሕይወት መሆኗን ተናግሮላታል::

ቅዱስ ዮሐንስ በራእዩ ጥንተ ጠላት የሆነው ዲያብሎስ በንጉሡ ሄሮድስ አድሮ በእመቤታችን በድንግል ማርያም ላይ ያደረሰውን መከ ራና ችግር አስመልክቶ ሲገልጥ "እባቡም ሴቲቱ በወንዝ እንድትወሰድ ሊያደርግ ወንዝ የሚያህልን ውኃ ከአፉ በስተኋላዋ አፈሰሰ" (ራእ. 12÷15) በማለት ተናግሮአል:: መጻሕፍት አምላካውያት በየገጻቸውና በየዓምዳቸው ችግርን፣ ፈተናን፣ መከራን፣ ክፉ ሰዎችን እንዲሁም ብዙኃ ሠራዊትን በወንዝ፣ በውኃ፣ በባሕር ምሳሌነት ይገልጻሉ:: ለዚህም "በእሳትና በውኃ መካከል አሳለፍከን" (መዝ. 65÷12)፤ "... እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ባይሆን ሰዎች በእኛ ላይ በተነሡ ጊዜ÷ ቁጣቸው በላያችን

(437) *መዝሙረ ዳዊት ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 325-326::*
(438) *ቅዱስ ያሬድ መጽሐፈ ድጓ፣ ገጽ 384::*

በነደደ ጊዜ÷ ... በዚያን ጊዜ ውኃ ባሰጠመን ነበር÷ በነፍሳችንም ላይ ፈሳሽ ባለፈ ነበር፤ በዚያን ጊዜ የጕርፉ ውኃ በነፍሳችን ላይ ባለፈ ነበር:: ለጥርሳቸው ንክሻ ያላደረገን እግዚአብሔር ይባረክ:: ነፍሳችን እንደ ወፍ ከአዳኞች ወጥመድ አመለጠች፤ ወጥመድ ተሰበረ እኛም አመለጥን" (መዝ. 123÷2-7)፤ "እጅህን ከአርያም ላክ አድነኝም:: ከብዙ ውኆች÷ አፋቸውም ምናምንን ከሚናገር ..." (መዝ. 143÷7-8) የሚሉት ቃላተ መጻሕፍት በቂ ማስረጃዎችና ምስክሮች ናቸው::

ስለዚህም እመቤታችን ድንግል ማርያም ሰይጣን በሄሮድስ ሠራዊት አድሮ በሞት ወንዝ ሊወስዳት በከፋት በተነሣባት ጊዜ "ወረድኣታ ይእቲ ምድር፤ ምድሪቱም ሴቲቱን ረዳቻት" (ራእ. 12÷16) እንዳለ ወላዲተ አምላክ ወደ ምድረ ግብፅ ያደረገችው የስደት ጉዞ ክፉኛ የሚያሳድዷትን ሠራዊተ ሄሮድስን በማስቀረቱ ምድሪቱ የሄሮድስ ሠራዊት የሰበቁባትን ጦርና የሳሉባትን የመከራ ስለት እንድታልፍ ረዳቻት፣ አገዘቻት፣ ሰወረቻት፣ ሸሸገቻት ማለት ነው:: በመጨረሻም በዚህ ታላቅና ድንቅ ራእይ ላይ "ዘንዶውም በሴቲቱ ላይ ተቈጥቶ የእግዚአብሔርን ትእዛዛት የሚጠብቁትን የኢየሱስም ምስክር ያላቸውን ከዘርዋ የቀሩትን ሊዋጋ ሄደ፤ በባሕርም አሸዋ ላይ ቆመ" (ራእ፤ 12÷17) የሚል ታላቅ ኃይለ ቃል ተጽፏል:: ይህም ኃይለ ቃል ልዑስ ባሕርይ እግዚአብሔር አስቀድሞ "በአንተና በሴቲቱ፣ በዘርህና በዘርዋ መካከል ጠላትነትን አደርጋለሁ፤ እርሱ ራስህን ይቀጠቅጣል አንተም ሰኰናውን ትቀጠቅጣለህ" (ዘፍ. 3÷15) ሲል በቅድስት ኦሪት ከተናገረው አምላካዊ ቃል ጋር በምሥጢር ይገናዘባል::

ከላይ የጠቀስነው ገጸ ንባብ ምሥጢራዊ ትርጓሜ ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም የሴቲቱ (የእመቤታችን) ዘር ከሆነው ከጌታችን ከኢየሱስ ክርስቶስ በፈሰሰው ማየ ገቦ (የቀኝ ጐን ውኃ) ተጠምቀው፣ ሀብተ ወልድ አግኝተው፣ ስመ ክርስትናን አጽንተው፣ በመንፈስ ልደት ከብረው፣ በሐዲስ ተፈጥሮ ታድሰውና ተቀድሰው የዳኑ ምእመናን ሁሉ



የጸጋ እናት መሆኗን በግልጥ ይመሰክራል:: ከዚህም ሌላ ይህ ኃይለ ቃል ዘንዶ የተባለው ጠላት ዲያብሎስ በልጇ በወዳጇ በኢየሱስ ክርስቶስ አምላክነት፣ አዳኝነት፣ ሕይወትነትና ፈራጅነት አምነው፤ እንዲሁም በእርሷ እናትነት፣ አማላጅነትና ቃል ኪዳን ተማጽነው፣ ሃይማኖተ ወንጌልን አጽንተው፣ ምግባረ ወንጌልን ይዘው የሚኖሩ ክርስቲያኖችን እስከ ዕለተ ምጽአት ድረስ ክፉኛ እንደሚቃወማቸውና እንደሚያሳድዳቸውም ያመለክታል:: ይልቁንም ደግሞ ይህ ጽኑ የዲያብሎስ ውጊያ የሚበረታውና የሚያይለው ዘንዶው በአሸዋ ላይ በቆመ ጊዜ መሆኑን ቅዱስ ዮሐንስ በአጽንኦት ገልጾአል:: ስመሆኑ "በባሕርም አሸዋ ላይ ቆመ" ማለት ምሥጢራዊ ትርጓሜው ምንድን ነው?

በቅዱሳት መጻሕፍት ትርጓሜ ምሥጢር መሠረት ይህ ዓለም በባሕር ይመሰላል:: ምክንያቱም በባሕር ውስጥ ደጋግ ፍጥረታትም ክፉ አራዊትም አብረው እንዳሉ ሁሉ፤ በባሕር ዓለምም በጐዎችና ክፉዎች፣ ኃጥአንና ጻድቃን፣ አማንያንና ከሐድያን በአንድነት ይኖራሉና:: ዳግመኛም ባሕር ማዕበል፣ ጽኑ ነፋስና ሞገድ እንደማይለየው፤ እንዲሁም ይህ ዓለም ኃዘንና ደስታ፣ ማግኘትና ማጣት፣ መውደቅና መነሣት፣ መውጣትና መውረድ፣ መከራና ችግር ይፈራረቁበታል:: በአጠቃላይ በባሕር የተመሰለው ይህ ዓለም በሁከት የተመላ ነው:: ሌላው ምሥጢር ደግሞ ባሕር ከምልዓቱ ሲጎድል በዳሩ ብዙ አሸዋ እንዲታይ፤ እንደዚሁም ምእመናን ከጽንዐ ሃይማኖት ተለይተው ወጥተው፣ ከገቢረ ጽድቅ ርቀው ምልዓተ እምነታቸው በጐደለ ጊዜ ሕይወታቸው በባሕር ዳር እንዳለ አሸዋ ይሆናል:: በዚህን ጊዜም ዘንዶ የተባለው ዲያብሎስ በአሸዋማ ልቡናቸው ማለትም ጽንዐ ሃይማኖት በሌለው፣ ምሉዓት እምነት በጎደለውና ከገቢረ ጽድቅ በራቀው ልቡናቸው በቀላሉ ይነግሣል፣ ይሠለጥናል::

ይህንን አስመልክቶ መምህረ ቅዱሳን የሆነው መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በመዋዕለ ስብከቱ ሲያስተምር "ይህን ቃሌን ሰምቶ

የማያደርገው ሰው ሁሉ ቤቱን በአሸዋ ላይ የሠራ ሰነፍ ሰውን ይመስላል:: ዝናብም ወረደ ጐርፍም መጣ ነፋስም ነፈሰ ያንም ቤት መታው፣ ወደቀም፣ አወዳደቁም ታላቅ ሆነ" (ማቴ. 7÷26-27፤ ሉቃ. 6÷47-49) በማለት አስገንዝቧል:: ስለሆነም ጌታችን በዚህ ምሳሌያዊ ትምህርቱ ጽንዐ ሃይማኖት የሌለው ሕይወት መሠረት እንደሌለው ቤ ት ስለሚቆጠር የጥርጥር ነፋስ በነፈሰበት ጊዜ፣ የፈተና ዝናብ በወ ረደበት ጊዜና የክሕደት ጐርፍ በመጣበት ጊዜ ፈጥኖ ይወድቃል ማለትም በቶሎ ይስታል፣ ይክዳል ሲል ገልጾ ተናግሮአል::

ሌላው ደግሞ አምላከ እስራኤል ልዑል እግዚአብሔር አበ ብዙኃን (የብዙዎች አባት) የተባለውን ታላቁን የእምነት አባት ጻድቁ አብርሃምን በመንፈሳዊ በረከት በባረከውና በቃል ኪዳን ተስፋም ባከበ ረው ጊዜ "ዘርህንም እንደ ምድር አሸዋ አደርጋለሁ" ብሎታል:: (ዘፍ. 13÷16) ዳግመኛም "ወደ ሰማይ ተመልከት÷ ከዋክብትንም ልትቈጥራ ቸው ትችል እንደሆነ ቁጠር አለው:: ዘርህም እንደዚሁ ይሆናል አለው" (ዘፍ. 15÷5) ተብሎ በቅዱስ መጽሐፍ ተጽፏል:: (ዕብ. 11÷12)

ሊቃውንተ ቤተ ክርስቲያን በትርጓሜያቸው ልዑለ ባሕርይ እግዚአብሔር ለወዳጁ ለአብርሃም በሰጠው በዚህ አምላካዊ ቃል ኪዳን መሠረት ምድራዊ ነገርን ብቻ የሚያስቡና ሥጋዊ ሥራን የሚሠሩ ኃጥአን ልጆቹን በምድር አሸዋ፣ በአንጻሩ ደግሞ ሰማያዊ ነገርን የሚያስቡና መንፈሳዊ ሥራን የሚሠሩ ጻድቃን ልጆቹን በሰማይ ከዋክብት መስሎ እንደነገረው አመሥጥረው ገልጸዋል:: በዚህ ትርጓሜ መሠረት ቅዱስ ዮሐንስ በራእዩ "ዘንዶውም በባሕር አሸዋ ላይ ቆመ" ሲል የተናገረው ኃይለ ቃል በፍጻሜ ዘመን ዘንዶ የተባለው ዲያብሎስ ከመንፈስ ቅዱስ ተለይተውና ከገቢረ ጽድቅ ርቀው በገቢረ ኃጢአት ጸንተው በሚኖሩ ሰዎች ልቡና ነግሦና ሰልጥኖ የሚኖር መሆኑን በምሥጢር ያስረዳል፣ ያስገነዝባል::



እንግዲህ እኛም መጻሕፍት አምላካውያት በመተባበር እንደመሰ ከሩልን ከጽንዐ ሃይማኖታችን ሳንናወጥ፣ ከምልዓተ እምነታችን ሳንጐድል ወልድ ዋሕድ ብላ የፈጣሪያችን የኢየሱስ ክርስቶስን አምላክ ነትና አዳኝነት፣ እንዲሁም ምክንያተ ድኅነት፣ ወሠረተ ሕይወት የሆነችውን የእናቱን የድንግል ማርያምን እናትነትና አማላጅነት በምታምነውና በምታሳምነው ርትዕት ሃይማኖታችን ጸንተንና እስከ መጨረሻይቱ ሕቅታ ድረስ ታምነን ልንኖር ይገባል:: (ማቴ. 16÷18፤ 24÷13፤ 1ኛ ቆሮ. 3÷11፤ 16÷13፤ 1ኛ ጢሞ. 5÷8፤ 2ኛ ጢሞ. 4÷6-8፤ ዕብ. 3÷12-14፤ 13÷9)

ይልቁንም መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በወንጌለ መንግ ሥቱ "ስለዚህ ይህን ቃሌን ሰምቶ የሚያደርገው ሁሉ ቤቱን በዓለት ላይ የሠራ ልባም ሰውን ይመስላል:: ዝናብም ወረደ ጐርፍም መጣ ነፋስም ነፈሰ ያንም ቤት ገፋው÷ በዓለት ላይ ስለመሠረተ አልወደ ቀም::" (ማቴ. 7÷24-25፤ ሉቃ. 6÷47-48) ብሎ እንዳስተማረን ሠራዊተ አጋንንት እያፈራረቁ የሚያመጡብንን ፈተና በእምነት ተቋቁመን፣ በትዕግሥት ድል ለመንሣት እንድንችል ዘወትር በሕይወታችን ጽንዐ ሃይማኖትን፣ ምግባረ ወንጌልን አጽንተን ልንይዝና ገንዘብ ልናደርግ ይገባናል:: ምክንያቱም "ባታምኑ አትጸኑም" (ኢሳ. 7÷9) ተብሏልና::

ይህ ከሆነ ደግሞ ሐዋርያው ቅዱስ ጳውሎስ "እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ከሆነ ማን ይቃወመናል?" (ሮሜ 8÷31) እንዳለው በክንፈ ረድኤቱ ጠብቆ፣ በጽላሎተ ረድኤቱ ከልሎ፣ በጸጋው ያከበረንንና ምርኩዘ ጻድቃን የሆነውን አምላክ "ዘአዝኃንከ እምኔነ ማዕበላተ ውኂዛተ መናፍስት:: ዘኮንከነ መርሶ ሕይወት እሙስና፤ ነፋሳት እየነቀነቁ ያመጡትን የጐርፉን ፈሳሽነት ጸጥ ያደረክልን ማለትም ሰይጣናት አሠርተዋቸው ኃጣውእ ያመጡትን ፍዳ ከእኛ ያራቅህልን፤ አንድም አጋንንት እየቀሰቀሷቸው መናፍቃን የሚያመጡብንን የጥርጥርና የክሕደት ሁከት ያስወገድክልን፤ ከጥፋት አድነህ የሕይወት ወደብ የሆንከን አንተ ነህ[439] እያልን ሲቁ "ሐመርነ ዘኢይቀርቦ ሞገድ፤

[439] መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 32-33::

ማዕበል ሞገድ የማይቀርበው የሕይወት መርከባችን»(440) ሲል ያመሰገነውን አምላካችንን ዘወትር በደስታ ተሞልተን ለማመስገን እንችላለን::

በአጠቃላይ ክብረ ቅድስት ድንግል ማርያምን አስመልክቶ እስካሁን ድረስ በዝርዝር የተመለከትነው ሰማያዊው መልአክ ቅዱስ ገብርኤል በዕለተ ብሥራት የሰበከውን አማናዊ ቃለ ውዳሴና ቃለ ፍሥሐ፤ እንዲሁም ደግሞ ከምድራውያን ደቂቀ አዳም የመጀመሪያዋ የአዲስ ኪዳን ምስክር የሆነችው ቅድስት ኤልሳቤጥ በመንፈስ ቅዱስ ተቃኝታ የተናገረችውን ልዩ ጣዕመ ውዳሴና ልጇ መጥምቀ መለኮት ቅዱስ ዮሐንስ የሰጠውን አማናዊ ምስክርነት መሠረት ያደረገና ከነገረ ድኅነት ጋር ያገናዘበ መሆኑን ልብ ይሏል:: በዚህም ለወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም ጸጋና ክብር፣ ውዳሴና ቅዳሴ ምንጩና መሠረቱ የምስጋናና የክብር ባለቤት የሆነው ልዑል ባሕርይ እግዚአብሔር መሆኑን ይገነዘቧል::

## 5.2 የመጻሕፍተ ቅዳሴያት አስተምህሮ

በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን እመቤታችን ቅድስት ድንግል ማርያም መልዕልተ ፍጡራን ማለትም በሰማይና በምድር ካሉ ፍጥረታት ሁሉ በላይ ሆና ትከበራለች:: ይኸውም ልዑል ባሕርይ እግዚአብሔር ተወዳዳሪና ተነጻጻሪ በሌለው ፍጹም ንጽሕናዋና ቅድስናዋ ለእናትነት ስለመረጣት፣ ለተዋሕዶ ስላዘጋጃትና ለድኅነተ ዓለም ልዩ መሣሪያ አድርጎ ፍጹም ስላከበራት ነው:: ይህንን ድንቅ ምሥጢር አስመልክቶ የቤተ ክርስቲያናችን ቅዳሴያት አምልተውና አስፍተው ያስተምራሉ:: ለአብነት ያህል መጠነ ሰፊ ከሆኑት የሥርዓተ ቅዳሴ ገጸ ንባባት መካከል ብንመለከት «ለማርያም ድንግል ንጽሕት ሠምራ አብ ወአሠርገዋ ደብተራ ለማኅደረ ፍቁር ወልዱ፤ ንጽሕት በድንግልና፣ ሥርጉት በቅድስና፣ ክብርት በልዕልና የምትሆን እመቤታችንን ልዑለ

(440) አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ፣ *መጽሐፈ ሰዓታት*፣ ገጽ 411::



ባሕርይ እግዚአብሔር ለልጁ እናት እንድትሆን መረጣት፣ ወደዳት:: ለልጁ ማደሪያነትም በንጽሕና፣ በቅድስና አስጌጣት»(441) ይላል::

ከዚህም ጋር ዘርፈ ብዙ የሆነውን የድንግል ማርያምን ሁለንተናዊ ዜና ሕይወትና ፍጹም ክብር የሚናገረው የእመቤታችን ቅዳሴ «ንትነሣእ በፍርሃተ እግዚአብሔር ከመ ያስብያ ወንወድሳ ለምልእተ ውዳሴ:: እንዘ ንብል ኦ ምልእተ ጸጋ:: ኦ ሙኃዘ ፍሥሐ÷ ፈድፋደ ብኪ ግርማ ራእይ ዘየዓቢ እምኪሩቤል እለ ብዙኃት አዕይንቲሆሙ ወሱራፌል እለ ፮ቱ ክነፊሆሙ፤ ፈሪሃ እግዚአብሔርን ምርኩዝ አድርገን እንነሣ÷ ምስጋናን የተመላች እመቤታችንን ፈጽመን እናገናት፣ እናመስግናት ዘንድ፤ አንድም ጸጋ ሰማያዊን፣ ጸጋ ምድራዊን የተመላሽ፣ ደስ የሚያሰኝ ጌታ መገኛ የምትሆኚ ድንግል ሆይ ደስ ይበልሽ እያልን እናከብራት ዘንድ እንነሣ:: ዓይናቸው ብዙ ከሚሆኑ ከኪሩቤል፣ ክንፋቸው ስድስት ከሚሆን ከሱራፌል ይልቅ የመወደድ ግርማ፣ የባለሟልነት ክብርና ሞገስ አለሽ»(442) በማለት ከሰማያውያን ቅዱሳን መላእክትና ከምድራውያን ደቂቀ አዳም ሁሉ በላይ የተለየ ፍጹም ክብር እንዳላት በግልጽ ይመሰክራል::

ይልቁንም ደግሞ በኦርቶዶክሳዊ ሥርዓተ ቅዳሴ ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም ልዩ የሆነ የክብር ሥፍራ የሚሰጣት በነገረ ድኅነት ውስጥ ባላት መሠረታዊ ድርሻና ከፍተኛ አስተዋጽኦ አማካይነት ነው:: የቤተ ክርስቲያናችን ቅዳሴያት እመቤታችን ምድራውያንና ሰማያውያን የታረቁባት፣ ግዙፉን ከረቂቃን ጋር የተገናኙባትና አንድ የሆኑባት የሕይወትና የጽድቅ መሰላል መሆኗን በስፋት ያስረዳሉ:: ዳግመኛም ለነገረ ድኅነት መሠረት የሆነው ይህ የድንግል ማርያም ልዩ ጸጋ በኦርቶዶክሳውያን ክርስቲያኖች ዘንድ ምዕራገ ጸሎት እንድትባል አድርጓታል::(443) በዚህም መሠረት ካህናትና ምእመናን

(441) *መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 84::
(442) *መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 225::
(443) *መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 81፣ 234:: ቅዱስ ያሬድ፣ "አንቀጸ ብርሃን"፣ 402፣ 412:: *ወንጌል ቅዱስ ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 458-459:: Daniel, *Blessed Virgin Mariam*, 121.

ዘወትር አማላጅነቷን፣ ከልጇ ከወዳጇ ከኢየሱስ ክርስቶስ የተሰጣትን የምሕረት ቃል ኪዳን ጥግ አድርገው ይኖራሉ።

ይህንን አማናዊ ጸጋና ክብር በመግለጥ የቤተ ክርስቲያናችን ሥርዓተ ጸሎት "ኦ በግዐ ዘአርያም በርእሰ ደብረ ጽዮን ዘቆምከ ኢትፍልጠነ እምኩብካበ ቅዱስ መርዓከ። ኢተዘኪረከ ለበላነ ወአናኅስዮከ ጌጋየነ በምሕረትከ ተዘከረነ፥ እንበለ ምሕረትከሰ አልቦ ዘይድኅን። ... ስማዕ ጸሎተ ኵሉ ዘሥጋ በእንተ ማርያም ምልእተ ጸጋ ...፤[444] በጽዮን ተራራ ራስ የቆምህ አማናዊ በግ ኢየሱስ ክርስቶስ ሆይ ከሙሽርነትህ ሠርግ አትለየን። በደላችንን ሳታስብ ኃጢአታችንን አቃለህ በቸርነትህ አስበን። ያለ ምሕረትህ ግን የሚድን የለም። ... የሥጋውያንን ሁሉ ጸሎት ጸጋን ስለ ተመላች ስለ ድንግል ማርያም ብለህ ስማ" በማለት ለወላዲተ አምላክ የተሰጠው ቃል ኪዳን የማይታጠፍና አማናዊ መሆኑን አስረግጦ አስገንዝቦአል።

ሊቁ አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫም ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም በግዐ ሕይወት የተባለ ጌታን ያስገኘች አማናዊት ምክንያተ ድኅነት መሆኗን ሲገልጥ "አንቲ ውእቱ ለይስሐቅ ደብረ መዓዛሁ፤ እንተ ፈፈይኪ በግዐ ዘእጉዝ በዕፀ ሳቤቅ አቅርንቲሁ"[445] በማለት መስክሮላታል። ኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያናችንም ይህንን ጽኑ እምነቷንና አማናዊ ትምህርቷን እመቤታችን የምሕረት እናት ሆና በቃል ኪዳን መክበሯን በሚገልጡት ቅዱሳት ሥዕላቶቿ ሁሉ ታስተላልፋለች።

በቤተ ክርስቲያናችን የቅዳሴ ሥርዓት ጊዜ የሚጸለየው የዕጣን ጸሎት የእመቤታችንን የአማላጅነት ጸጋ በሚገባ ይገልጻል። "... እግዝእትነ ወላዲተ አምላክ ዐረገ ዘንተ ዕጣነ፥ ወዘንተ ጸሎተነ። ወዘንቶ ማኅቶተነ። ወዘንተ መሥዋዕተነ፤ አምላክን የወለድሽ እመቤታችን ይህን ዕጣናችንን አሳርጊልን። ይህንን ጸሎታችንን፣ ይህንን መብራታችንን፣

(444) "መስተብቍዕ ዘሙታን"፣ *መጽሐፈ ቅዳሴ*፣ (አዲስ አበባ፤ አክሱም ማተሚያ ቤት፣ 1993 ዓ.ም.)፣ ገጽ 496-497።
(445) አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ [Abba Giyorgis of Gascha]፣ *ዕንዚራ ስብሐት ["The Lyre of Glory"]*፣ ገጽ 2።





**ሥዕል 17:- እመቤታችን የምሕረት ቃል ኪዳን እንደተቀበለች**

"ወካዕበ ተማኅፀነ በማርያም እምከ። እንተ ይእቲ እግዝእትነ ወመድኃኒትነ ወትምክሕተ ዘመድነ በወላዲተ ዚአከ። እስመ አንተ ትቤላ ዘገብረ ተዝካረኪ ወዘጸውዐ ስመኪ ሕይወተ ዘለዓለም የሐዩ።"

"ዳግመኛም በእናትህ በማርያም ተማፅነናል። ይህችውም አንተን በመውለድ እመቤታችንና መድኃኒታችን የባሕርያችን መመኪያ ናት። አንተ መታሰቢያሽን ያደረገ፣ ስምሽንም የጠራ የዘላለም ሕይወት መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳል ብለሃታልና።"

(መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 445)

ይህን መሥዋዕታችንን አሳርጊልን:: ... ወቡሩክ ወልድ ዋሕድ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘተወልደ እምእግዝእትነ ማርያም ቅድስት ድንግል ለመድኃኒተ ዚአነ፤ እኛን ለማዳን ከእመቤታችን የተወለደ፣ ተቀዳሚ ተከታይ የሌለው ወልድ ክቡር ምስጉን ነው::»(446) በማለት ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም ምዕራገ ጸሎት የመሆኗን ምሥጢር ከነገረ ድኅነት ጋር በማያያዝ በአጽንኦት ይመሰክራል::

ሌላው ደግሞ የቅዱስ ያዕቆብ ዘሥሩግ ቅዳሴ የቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያምን የአማላጅት ቃል ኪዳን መማጸኛ በማድረግ ሲናገር «ወካዕበ ተማኅፀነ በማርያም እምከ እንተ ይእቲ እግዝእትነ ወትምክህተ ዘመድነ በወላዲተ ዚአከ:: እስመ እንተ ትቤላ ዘገብረ ተዝካረኪ ወዘጸውዓ ስመኪ ሕይወተ ዘለዓለም የሐዩ፤ ዳግመኛም በእናትህ በማርያም ተማጽነናል:: ይህችውም አንተን በመውለድ የባሕርያችንና የነገዳችን መመኪያ እመቤታችን ናት:: አንተ ስምሽን ጠርቶ፣ ዝክርሽን የዘከረ የዘላለም ሕይወት መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳል ብለሃታልና»(447) ይላል:: (ማቴ. 10÷40-42) በዚህም የወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም ምልጃ የቅዱሳን ሁሉ ጸሎትና ምልጃ አክሊል (ጉልላት) ነው የምንለው በምሥጢረ ድኅነት ውስጥ ያላትን ሰፊ ድርሻ መሠረት አድርገን መሆኑን ይገነዘቧል::

ይልቁንም ደግሞ ምልዕተ ጸጋ፣ ምልዕተ ውዳሴ፣ ምልዕተ ክብር የሆነችው የእመቤታችን ቅዳሴ ሐዳፌ ነፍስ ከላይ የገለጥነውንና ቤተ ክርስቲያናችን ስለ ድንግል ማርያም የአማላጅነት ቃል ኪዳን ያላትን ቀጥተኛ አስተምህሮ ከዚህ እንደሚከተለው ያስረዳል::

*ኦ ድንግል ተዘከሪ ኀበ መዘክር ዘኢይደረስበ ኵሉ፤ ድንግል ሆይ ትንኝን እንኳን ከማይዘነጋ ልጅሽ ዘንድ አሳስቢልን::*

*ተዘከሪ ድንግል ልደቶ እምኔኪ ዘተወልደ በቤተ ልሔም፤ ድንግል ሆይ በቤተ ልሔም ካንቺ የተወለደውን መወለድ አሳስቢልን::*

(446) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 66::
(447) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 445::



*ወዘተጠብለለ በአጽርቅት፤ ድንግል ሆይ በጨርቅ የተጠቀለለውን መጠቅለል አሳስቢልን::*

*ለስተማወቅዎ ለስተንፋስ እድግ ወላህም በመዋዕለ ቍር፤ ድንግል ሆይ ብርድ በጸናበት ወራት አህያና ላም እስትንፋሳቸውን ያሟሟቁትን አሳስቢልን::*

*ተዘከሪ ድንግል ንገዶተ ዘምስሌኪ እንዘ ትጐይዩ ምስሌሁ እምሀገር ለሀገር በመዋዕለ ሄሮድስ ርጉም፤ ድንግል ሆይ በንጉሥ ሄሮድስ ዘመን ከሀገር ወደ ሀገር ካንቺ ጋር መሰደዱን አሳስቢልን::*

*ተዘከሪ ድንግል አንብዓ መሪረ ዘውኅዘ እምአዕይንትኪ ወወረደ ዲበ ገጸ ፍቁር ወልድኪ፤ ድንግል ሆይ ከዓይኖችሽ በልጅሽ፣ በወዳጅሽ ፊት የወረደውን ጽኑዕ ዕንባ አሳስቢልን::*

*ተዘከሪ ድንግል ረኀበ ወጽምዓ ምንዳቤ ወኀዘነ ወኵሎ ዓፀባ ዘበጽሐኪ ምስሌሁ፤ ድንግል ሆይ የተራብሽውን መራብ፣ የተጠማሽውን መጠማት፣ የተቀበልሽውን ጸዋትወ መከራ፣ ያዘንሽውን ኃዘን፣ ከእርሱ ጋራ ያገኘሽን ጭንቅ ሁሉ አሳስቢልን::*

*ተዘከሪ ሣህለ ወእኮ ተኃሥሦ:: ተዘከሪ ምሕረተ ወእኮ መዓተ፤ ጥፋትን ያይደለ ይቅርታን አሳስቢልን፤ መዓትን (ከእኔ ሂዱ) ያይደለ ምሕረትን (ወደ እኔ ኑ) ማለትን አሳስቢልን::*

*ተዘከሪ ለኃጥአን ወእኮ ለጻድቃን፤ ለጻድቃን ያይደለ ለኃጥአን አሳስቢልን::*

*ተዘከሪ ለርሱሐን ወእኮ ለንጹሐን፤ ንጹሐን ነን ለሚሉት ያይደለ ርሱሐን (ርኩሳን፣ በደለኞች) ነን ለሚሉ አሳስቢልን::*(448)

(448) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 266-270::

ከላይ የገለጥነው የቅዳሴ ክፍለ ንባብ እመቤታችን ቅድስት ድንግል ማርያም ወላዲተ አምላክ መሆኗን በጉልህ ከማሳየቱም ሌላ በክብረ ወሊድ ላይ የተሰጣትን የክብረ ድንግልና ጸጋም አስረግጦ ይመሰክራል:: ይኸውም «ቅ ድንግል፣ እዘከሬ ድንግል» የሚሉት የገጸ ንባባቱ መነሻ ኃይለ ቃላት እመቤታችን ወትረ ድንግል (ዘለዓለማዊት ድንግል) መሆኗን ያስረዳሉ፣ ያስገነዝባሉ::

የምሥጢረ ሥጋዌ አንኳር ምሥጢር የሆነውን የወላዲተ አምላክን ዘለዓለማዊ ድንግልና አስመልክቶ ሁለንተናዊ ክብሯን ከብሉያትና ከሐዲሳት እያስማማ የሚገልጸው የቅዳሴ ክፍል «በአማን ነጸረ እግዚአብሔር አብ እምሰማይ ምሥራቀ ወምዕራበ ሰሜነ ወደቡበ አስተንፈሰ ወአጼነወ:: ወኢረከበ ዘከማኪ፤ ወሠምረ መዓዛ ዚአኪ ወአፍቀረ ሥነኪ፤ ወፈነወ ኀቤኪ ወልዶ ዘያፈቅር»(449)፤ ልዑለ ባሕርይ እግዚአብሔር በልዕልና ሆኖ አራቱን ማዕዘን በእውነት ተመለከተ፣ መረመረ:: እንዳንቺ ንጽሕት በድንግልና፣ ሥርጉት በቅድስና፣ ክብርት በልዕልና ሆና የተዘጋጀች አላገኘም:: ስለዚህም መዓዛ ንጽሕናሽን፣ መዓዛ ቅድስናሽን ወደደ:: ሥጋሽንም ለተዋሕዶ መረጠ:: የሚወደውን፣ የሚወልደውን አንድያ ልጁን ወደ አንቺ ላከ በማለት በአጽንኦት ይመሰክራል::

ሌላው ደግሞ ሊቀ ነቢያት ሙሴ በሲና ተራራ ዕፀ ጳጦስን በነበልባለ እሳት ሳትቃጠል ማየቱ አማናዊቷ ዕፅ እመቤታችን ወልደ እግዚአብሔር ከእርሷ ሰው በሆነ ጊዜ ማኅተመ ድንግልናዋ አለመለወጡን በምሥጢር ያጠይቃል:: ይህም ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም ቅድመ ፀኒስ፣ ጊዜ ፀኒስ፣ ድኅረ ፀኒስ፤ ቅድመ ወሊድ፣ ጊዜ ወሊድ፣ ድኅረ ወሊድ ጽንዕት በድንግልና፣ ሥርጉት በቅድስና፣ ክብርት በልዕልና እንደሆነች ያረጋግጣል:: ከዚህም ጋር ሊቁ «እስመ ብኪ ጠለ ተአምር እንተ ርእየ ነጸረ ጌዴዎን ኀበ ሰፍሐ አምሳሊኪ ፀምረ፤ ንጽሕት በድንግልና፣ ሥርጉት በቅድስና፣ ክብርት በልዕልና እመቤታችን ድንግል ማርያም ሆይ ጠለ

(449) *መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 226::



መለኮት በኅቱም ማኅፀንሽ በማደሩ የምስጋናሽን ታላቅነት ታላቁ የእግዚአብሔር ሰው ጌዴዎን በዘረጋት ፀምር ላይ ተመለከተ»(450) ለምሳሌ ያህል ብንመለከት ከቤተ ክርስቲያናችን ሥርዓተ ቅዳሴ ክፍለ ንባብ መካከል አንዱ «... ኢየሱስ ክርስቶስ ወልደ እግዚአብሔር ጸባዖት ወወልደ ማርያም ንጽሕት በድንግልና ኅሊና ወበድንግልና ሥጋ ኅትምት ለዓለመ ዓለም»(451)፤ ቅድመ ዓለም ከባሕርይ አባቱ ከአብ የተወለደ የእግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ክርስቶስ ድኅረ ዓለም በድንጋሌ ሥጋ፣ በድንጋሌ ነፍስ ከጸናች ከእመቤታችን ከቅድስት ድንግል ማርያም ባሕርይ የተወለደ የድንግል ማርያም ልጅ ነው በማለት ወላዲተ አምላክ ወትረ ድንግል (ዘለዓለማዊት ድንግል) መሆኗን በአጽንኦት ይገልጻል፣ ይመሰክራል::

በዚህም መሠረት ኦርቶዶክሳውያን መጻሕፍተ ውዳሴያትና ቅዳሴያት በመተባበር እመቤታችንን «ሀሊዶ ውስተ ሰብሐተ ድንግልናኪ ኦ ማርያም ድንግል ፍጽምት»(452) በድንጋሌ ሥጋ፣ በድንጋሌ ነፍስ ፍጽምት፣ ኅትምት፣ ጽንዕት የምትሆኚ እመቤታችን በኅቱም ድንግልና ጸንተሽ ብትገኚ ላንቺ የተሰጠ ጸጋና ክብር ፍጹም ነው» እያሉ ዘወትር ያከብሯታል፣ ያመሰግኗታል:: ኢትዮጵያዊው ሊቅ አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም ድንግልናዋ በእናትነት ሳይሻር፣ እናትነቷም በድንግልና ሳይለወጥ የመኖሯን ልዩ ምሥጢር ሲያደንቅ «ናሁኬ ፩ አምላክ ተወልደ እምድንግል እንዘ ኢይትነሠት ማኅተመ ድንግልናሃ:: አልቦ እመ ሰማዕነ ከመ ወለደት ድንግል በኢረካቤ ዘብእሲ:: ... ናሁኬ ፩ ትሕትና:: እንቅዓ ሐሊበ እምእጥባተ ወለት እንተ ኢተአምር ብእሴ:: ወአኃዞን ለአሙንቱ አጥባት ወአብቀወ አፉሁ ለወሊወ ሐሊበን:: ናሁኬ ፩ መንክር:: እስመ ለሊሁ እንቅዓ ወለሊሁ ጠበወ»(453) ብሏል::

(450) አባ ጽጌ ድንግል፣ «ማኅሌተ ጽጌ»፣ ገጽ 612:: ሱኑትዩ «ሥላሴ በተዋሕዶ»፣ *ሃይማኖተ አበው*፣ ገጽ 499::
(451) *መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 157::
(452) *ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው*፣ ገጽ 48::
(453) አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ [Abba Giyorgis of Gascha]፣ *መጽሐፈ ምሥጢር* [*"The Book of Mystery"*]፣ ገጽ 2-3::

ዳግመኛም ሌላው ሊቅ «ስብሐተ ድንግልናኪ ዘዕፌ ይነግር አፉዮ»[454]፤ ማኅደረ መለኮት ድንግል ማርያም ሆይ አንደበቴ ዘለዓለማዊ የሚሆን የድንግልናሽን ፍጹም ክብር ዘወትር ይናገራል፣ ይመሰክራል» ሲል ክብረ ድንግልናዋ ለዘወትር ምስጋናችን ጌጥ፣ ፈርጥ መሆኑን ገልጾ አስረድቷል:: ሊቁ ቅዱስ ባስልዮስ ዘቂሳርያም በቅዳሴው «ሃሌ ሉያ ቅድስት ወኀሪት ወላዲተ አምላክ ማርያም ድንግል፤ ቅድመ ዓለም በኅሊና አምላክ ታስባ ለኖረች፣ ንጽሕት በድንግልና፣ ሥርጉት በቅድስና፣ ክብርት በልዕልና ለሆነችው፣ ለመለኮት ማደሪያነት ለተመረጠችውና ቀዳማዊውን አምላክ ለወለደች ለእመቤታችን በእውነት ምስጋና ይገባታል»[455] በማለት ተናግሮአል:: ስለሆነም ኦርቶዶክሳውያን ክርስቲያኖች ቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያም በክብረ ወሊድ ላይ ክብረ ድንግልና የተጎናጸፈች እናትም ድንግልም በመሆኗ ይህንን ታላቅ ክብርና ልዩ ጸጋ በዘወትር ምስጋናቸው ሁሉ በግልጥ ይመሰክሩላታል::[456]

ሊቃውንተ ቤተ ክርስቲያን ለአእምሮ ረቆ፣ ለአንደበት ርቆ፣ ዕፁብ ለተነግሮ ሆኖ የሚኖረውን የወላዲተ አምላክን ዘለዓለማዊ ድንግልና በተለያየ ዓይነት ምሳሌ ለመግለጥና ለማስረዳት ሞክረዋል:: ለአብነት ያህል ብንጠቅስ በክፍል 4.1.6.2 ላይ በስፋት እንደገለጥነው የሰባክያን አክሊልና የአትሮንስ ንጉሥ በመባል የሚታወቀው 'ወርቃማው' የቤተ ክርስቲያናችን አባት ሊቁ ቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ የቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያምን ዘለዓለማዊ ድንግልና አስመልክቶ «የበኵር ልጅዋን እስክትወልድ ድረስ ዮሴፍ አላወቃትም» የሚለውን የማቴዎስ 1÷25 ገጸ ንባብ በዘመኑ ለነበረው ንጉሥ አርቃድዮስ በተረጐመለት ጊዜ በአጠገቡ የነበረችው ሥዕለ ማርያም «ሠናየ ተናገርከ ኦ ዮሐንስ አፈወርቅ፣ ሠናየ ተናገርከ ኦ ዮሐንስ ልሳነ ወርቅ፣ ሠናየ ተናገርከ ኦ ዮሐንስ አፈ ዕንቍ»[457] እያለች አመስግናዋለች፣ መርቃዋለች፣ ባርካዋለች::

(454) ዐዔ ዘርዐ ያዕቆብ እና ዐዔ ናዖድ፣ «መልክዐ ማርያም»፣ ገጽ 535::
(455) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 358::
(456) «መስተብቍዕ ዘሙታን»፣ ገጽ 498-501::
(457) ቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ፣ ድርሳን ዘቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ፣ ገጽ 12-13::



ከዚህም ጋር የፊት ወዝ ግምባርን ሳይለውጥና ሳያናውጥ ከሰውነት መውጣቱ፣ እንዲሁም ፀዳለ ብርሃን በመስተዋት ውስጥ አንዳችም መሰንጠቅና መሰበር ሳይኖርበት፣ ጉዳትም ሳይደርስበት ማለፉ ዋሕድ ቃለ እግዚአብሔር ከቅድስት ድንግል ማርያም በተዋሕዶ ሰው ሆኖ በተወለደ ጊዜ ማኅተመ ድንግልናዋ አለመለወጡን ያስረዳል፣ ያስገነዝባል:: በተጨማሪም አንድ ሰው በሌላ ሰው ፊት በቆመ ጊዜ ሁለንተናዊ አካሉን ዓይኑን ሳይቆጠቁጥና ሳይጐረብጥ እንዲያየው፤ ጌታም የእመቤታችንን ማኅተመ ድንግልናዋን ሳይለውጥና ሳያዛባ ባሕርይዋን በተዋሕዶ ፍጹም ባሕርዩ አድርጐ ተወልዶአል::

ዳግመኛም መድኀኒ ዓለም ኢየሱስ ክርስቶስ በኅቱም ማኅፀነ ድንግል ማርያም መወለዱ ኋላ በዕለተ ትንሣኤም በኅቱም መቃብር የተነሣ የሕይወት ባለቤት መሆኑን በምሥጢር ያመለክታል:: ከዚህም ጋር ጌታችን ከትንሣኤው በኋላ ቅዱሳን ሐዋርያት በጽርሐ ጽዮን ደጆቻቸውን ዘግተው ብቻቸውን ተቀምጠው ሳሉ በተዘጋው ደጅ መግባቱና በመካከላቸው መታየቱ የባሕርዩን ርቀት ከመግለጡም ሌላ ኅትምት በድንግልና ከሆነችው ከእመቤታችን ከቅድስት ማርያም መወለዱን በምሥጢር ያጠይቃል:: ይህንን አስመልክቶ ሊቁ ቅዱስ ዲዮስቆሮስ በቅዳሴው ሲያስረዳ «አመ ሣልስት ዕለት ተንሥአ እሙታን:: ወቦአ ኀበ ሀለዉ አርዳኢሁ ንዑዓን ወእስተርአዮሙ በጽርሐ ጽዮን፤ በሦስተኛው ቀን መቃብር ክፈቱልኝ፣ መግነዝ ፍቱልኝ ሳይል ከሙታን ተለይቶ ተነሣ:: ደቀ መዛሙርቱ ወዳሉበት በዝግ ቤት ገባ:: በዝግ ቤት ገብቶም በጽርሐ ጽዮን ታያቸው»[458] ብሏል::

ቀደም ብለን በክፍል 4.1.6 ላይ እንደገለጥነው በወርቃማው ዘመን ከተነሡት ቅዱሳን አበው መካከል ጀሮም የተባለው የቤተ ክርስቲያን አባት በዘመኑ ለነበረውና የእመቤታችንን ዘለዓለማዊ ድንግልና ለሚቃወመው ሔልቪዲየሳዊ የክሕደት ትምህርት የሰጠውን መጠነ ሰፊ ኦርቶዶክሳዊ ምላሽ ተመልክተናል:: ይህ አባት ረቂቅና

(458) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 451::

ጥልቅ በሆነው የነገረ ማርያም አስተምህሮው መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በኅቱም መቃብር መነሣቱና ኋላም በዝግ ቤት ገብቶ ለቅዱሳን ሐዋርያት መታየቱ፤ ዓለምን ለማዳን ሰው በሆነ ጊዜ የእመቤታችንን ማኅተመ ድንግልና ሳይለውጥ በኅቱም ድንግልና ተፀንሶ፣ በኅቱም ድንግልና መወለዱን ያረጋግጣል ሲል በአጽንኦት ተናግሮአል፣ መስክሮአል::(459)

የቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያምን ሁለንተናዊ ክብር ማለትም ወላዲተ አምላክነቷን፣ ዘለዓለማዊ ድንግልናዋን እንዲሁም በነገ ረ ድኅነት ውስጥ ያላትን ልዩ ሱታፌ አስመልክቶ በሥርዓተ ቅዳሴ ጊዜ ከቅዱስ ወንጌል ንባብ ቀደም ብሎ የሚጸለየው ቃለ ውዳሴ እንዲህ ሲል ይገልጻል:-

> *ተፈሥሒ ኦ ዘንስእለኪ ዳግና ኦ ቅድስተ ምልዕተ ክብር ድንግል በኵሉ ጊዜ ወላዲተ አምላክ እሙ ለክርስቶስ:: ድኅነተ ሥጋን፣ ድኅነተ ነፍስን አሰጭን ብለን የምንለምንሽ ንጽሕት፣ ጽንዕት፣ ኅትምት፤ ልዩ የምትሆኚ፣ ክብርን የተመላሽ፤ ቅድመ ወሊድ፣ ጊዜ ወሊድ፣ ድኅረ ወሊድ ድንግል የምትሆኚ አምላክን የወለድሽ የክርስቶስ እናቱ እመቤታችን ደስ ይበልሽ::*

> *አዕርጊ ጸሎተነ ዲበ መሰዕበት ኀበ ፍቁር ወልድኪ ከመ ይሥረይ ለነ ኃጣውኢነ፤ ምዕራገ ጸሎት እመቤታችን ሆይ ልመናችንን፣ ጸሎታችንን ወደ ልጅሽ ወደ ወዳጅሽ አሳርጊልን::*

> *ተፈሥሒ ኦ ዘወለድኪ ለነ ብርሃነ ጽድቅ ዘበአማን ክርስቶስሃ አምላክነ፤ እውነተኛ የሕይወት ብርሃን የሚሆን የባሕርይ አምላክ ፈጣሪያችን ክርስቶስን የወለድሽልን እመቤታችን ደስ ይበልሽ::*

(459) Malaty (Fr.), *St. Mary in the Orthodox Concept,* 23, 26-27. Carol, *Mariology,* vol. 2, 223. Getachew Haile (Professor), *The Mariology of Emperor Zara Yacob of Ethiopia,* 64.



> *ኦ ድንግል ንጽሕት ሰአሊ ለነ ኀበ እግዚእነ ከመ ይግበር ምሕረተ ለነፍሳቲነ ወይሥረይ ለነ ኃጣውኢነ፤ ንጽሕት፣ ቅድስት የምትሆኚ ድንግል ኃጢአታችንን ያስተሠርይልን ዘንድ ወደ ጌታችን ለምኚልን፣ አማልጅን::*

> *ተፈሥሒ ኦ ድንግል ማርያም ወላዲተ አምላክ ቅድስት ወንጽሕት:: ሰአሊት ዘበአማን በእንተ ዘመደ እጓለ እመሕያው፤ ለሰው ልጆች በእውነት አማላጅ የምትሆኚ አምላክን የወለድሽ ድንግል ሆይ ደስ ይበልሽ::*

> *ሰአሊ ለነ ቅድመ ክርስቶስ ወልድኪ ከመ ይጸግወነ ሥርየተ ኃጣውኢነ፤ ኃጢአታችንን ይቅር ይለን ዘንድ ከልጅሽ ከክርስቶስ ዘንድ አማልጅን፣ ለምኚልን::*

> *ተፈሥሒ ኦ ድንግል ንጽሕት ዘበአማን ንግሥትነ፤ በእውነት ንግሥት የምትሆኚ ንጽሕት፣ ድንግል ደስ ይበልሽ::*

> *ተፈሥሒ ኦ ምክሐ ዘመድነ፤ የባሕርያችን መመኪያ እመቤ ታችን ደስ ይበልሽ::*

> *ተፈሥሒ ኦ ዘወለድኪ ለነ ለአማኑኤል አምላክነ:: ፈጣሪያችን አማኑኤልን የወለድሽልን እመቤታችን ደስ ይበልሽ::*

> *ንስእለኪ ከመ ትዘከርነ ዓራቂት ዘበአማን ቅድመ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ከመ ይግበር ምሕረተ ለነፍሳቲነ ወይሥረይ ለነ ኃጣውኢነ፤ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ እውነተኛ አስታራቂ ሆነሽ አስበሽ ታሳስቢን ዘንድ እንለምንሻለን:: ኃጢአታችንን አስተሥርዮ ለነፍሳችንም ይቅርታን ያደርግ ዘንድ::(460)*

በኦርቶዶክሳውያን ዘንድ ልዩ ሥፍራ የሚሰጠው የእመቤ ታችን የቅድስት ድንግል ማርያም ክብር በሰማያዊው መልአክ በቅዱስ

(460) *መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 81::*

ገብርኤል ዜና ብሥራትና ጸጋ መንፈስ ቅዱስን በተመላች በቅድስት ኤልሳቤጥ ቃለ ውዳሴ ላይ የተመሠረተ መሆኑን አውስተናል። ይህንን አማናዊ ቃለ ውዳሴ አብነት፣ መሠረት በማድረግ ዘወትር በቅዳሴ ጊዜ ሠራዒው ካህንና ምእመናኑ እየተቀባበሉ ከዚህ የሚከተለውን ይጸልያሉ።

ይ.ካ. ቦአ መልአክ ኀቤሃ ወቆመ ቅድሜሃ ወይቤላ ተፈሥሒ ተፈሥሒ ተፈሥሒ ኦ ምልዕተ ጸጋ።
ይ.ሕ. እግዚአብሔር ምስሌኪ።
ይ.ካ. ቡርክት አንቲ እምአንስት።
ይ.ሕ. ወቡሩክ ፍሬ ከርሥኪ።
ይ.ካ. ተሰአሊ ለነ ኀበ ክርስቶስ ወልድኪ።
ይ.ሕ. ከመ ይሥረይ ለነ ኃጣውኢነ።

የዚህ ዐቢይ ቃለ ውዳሴ ምሥጢራዊ ትርጓሜም ከዚህ በታች ተገልጿል።

ይ.ካ. የእግዚአብሔር መልአክ ወደ እርሷ ገባ። ከፊቷም ቆሞ በነቢያት ትንቢት፣ በመላእክት ተልእኮ፣ ጸጋን አግኝተሻልና ጸጋን የተመላሽ እመቤታችን ሆይ ፈጽሞ ደስ ይበልሽ።

ይ.ሕ. ልዑለ ባሕርይ እግዚአብሔር ከሥጋሽ ሥጋ፣ ከነፍስሽ ነፍስ ነሥቶ በተዋሕዶ አንድ ባሕርይ ሆኗልና ደስ ይበልሽ።

ይ.ካ. ከሴቶች ተለይተሽ የተባረክሽ ነሽ። መርገመ ሥጋ፣ መርገመ ነፍስ የሌለብሽ፤ በረከተ ሥጋ፣ በረከተ ነፍስን እያማለድሽ የምታሰጪ ነሽ።

ይ.ሕ. የማኅፀንሽ ፍሬ መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ መርገመ ሥጋን፣ መርገመ ነፍስን የሚያርቅ፤ በረከተ



ሥጋ፣ በረከተ ነፍስን የሚያድል ቡሩክ፣ ምስጉን የባሕርይ አምላክ ነው።

ይ.ካ. ከልጅሽ ከወዳጅሽ ከክርስቶስ ዘንድ ለምኚልን፣ አማልጅን።

ይ.ሕ. ኃጢአታችንን ያስተሠርይልን ዘንድ በእውነት ለምኚልን።(461)

በኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን የቅዳሴ ሥርዓት ዘወትር የሚጸለየው የቅዱሳን ሐዋርያት አጠክንዮ ክብረ ቅድስት ድንግል ማርያም ከነገረ ድኅነት ጋር ያለውን ምሥጢራዊ አንድነት ሲገልጥ «... ዘሠምረ ይኩን ሰብአ በጽንዔ መዋዕል። ወነሥአ ሥጋ እማርያም እምቅድስት ድንግል ዘእንበለ ዘርዐ ብእሲ። ... ወእምዝ ሐመ ወሞተ በሥጋ። ወተንሥአ እሙታን በሣልስት ዕለት ወዐርገ ሰማያተ ኀበ አብ ዘፈነዎ። ወነበረ በየማነ ኃይሉ፤ ዓለም ሳይፈጠር አካል ዘእምአካል፣ ባሕርይ ዘእምባሕርይ የተወለደ፣ ተቀዳሚ ተከታይ የሌለው በዘመን፣ በክብር ከባሕርይ አባቱ ጋር አንድ የሚሆን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በኋለኛው ዘመን (አምስት ሺህ አምስት መቶ ዘመን ሲፈጸም) ዘርዕ ምክንያት ሳይሆነው ንዕድ፣ ክብርት ከምትሆን ከእመቤታችን ሥጋን ነሥቶ በተዋሕዶ ሰው ሆነ። ... ከዚህ በኋላ በፈቃዱ መከራ ተቀብሎ በሥጋ ሞተ። በሦስተኛው ቀን መቃብር ክፈቱልኝ፣ መግነዝ ፍቱልኝ ሳይል ከሙታን ተለይቶ ተነሣ። በብርሃን፣ በሥልጣን፣ በጌትነት፣ በይባቤ መላእክት በአርባኛው ቀን ወደ ላከው ወደ አብ በክብር ዐረገ። በአብ ዕሪና ማለትም አብን በሥልጣን መስሎ፣ ተካክሎ በፍጹም የጌትነት ክብር ኖረ።»(462) በማለት ይመሰክራል።

ከዚህ በተጨማሪ ደግሞ በቤተ ክርስቲያናችን ሥርዓተ አምልኮ ዘወትር የሚጸለየውና በቅዳሴ ጊዜም ከጸሎተ ወንጌል በፊት

(461) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 73፣86።
(462) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 105።

የሚደርሰው የኪዳን ጸሎት «ቅዱስ እግዚአብሔር ቅዱስ ኃያል ቅዱስ ሕያው ዘኢይመውት፤ ዘተወልደ እማርያም እምቅድስት ድንግል ተሣሃለነ እግዚኦ፤ ልዩ ገዢ፣ ልዩ ኃያል፣ ልዩ ሕያው በፈቃድህ እኛን ለማዳን ንዕድ፣ ክብርት ከምትሆን ከእመቤታችን ከቅድስት ድንግል ማርያም የተወለድክ አቤቱ ራርተህ ሥርየተ ኃጢአትን ስጠን»(463) በማለት ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም በነገረ ድኅነት ውስጥ ያላት ከፍተኛ ድርሻ ለአማላጅነት ክብሯ ምንጭና መሠረት መሆኑን በጉልህ ያሳያል፣ ያረጋግጣል። ከዚህ በተ ጨማሪም ይህን የእመቤታችንን የምልጃ ቃል ኪዳን መሠረት በማድረግ ከቤተ ክርስቲያናችን መጻሕፍተ ውዳሴያት አንዱ ባሕረ ምሕረት የሆነውን ልዑለ ባሕርይ እግዚአብሔር በወዳጁ በቅዱስ ዮሐንስ አማካይነት መንፈሳዊት እናት አድርጎ በጸጋ ስለሰጠን ስለ እናቱ ስለ ቅድስት ድንግል ማርያም ብሎ ይቅር እንዲለን ይማጸናል።(464)

ከላይ የገለጥነውንና በምሥጢረ ድኅነት ላይ የተመሠረተውን የእመቤታችንን ፍጹም ክብር አስመልክቶ የቅዳሴዋ መጽሐፍ «ኦ ማርያም በእንተዝ ናዐቢ ወናዐብየኪ። እስመ ወለድኪ ለነ መብልዐ ጽድቅ ዘበአማን ወስቴ ሕይወት ዘበአማን፤ አማናዊት እመቤታችን ክብርሽን፣ ገናንነትሽን እንናገራለን። ሥጋዊ ያይደለ መንፈሳዊ፣ አፍአዊ ያይደለ ውሳጣዊ፣ ምድራዊ ያይደለ ሰማያዊ፣ ጊዜያዊ ያይደለ ዘለዓለማዊ የሚሆን እውነተኛውን ምግበ ነፍስ ኅብስተ ሕይወት ቅዱስ ሥጋውን፣ እውነተኛ ውን መጠጥ ማየ ሕይወት ክቡር ደሙን አስገኝተሽልናልና»(465) ሲል ተናግሮላታል።

በመሆኑም ወላዲት አምላክ ድንግል ማርያም ፍሬ ሕይወት ጌታን እንበለ ዘርዕ፣ እንበለ ሩካቤ በማስገኘቷ አማናዊት በትረ አሮን መባሏን በክፍል 4.1.2 ላይ ተመልክተናል። ይህንን አስመልክቶም የቅዳሴዋ መጽሐፍ «ወኣዲ በትር አንተ ሠረጸት ወጸገየት ወፈረየት፤ ዳግመኛም

(463) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 24-25፣ 86።
(464) «መስተብቍዕ ዘእግዝእትነ ማርያም»፣ ገጽ 495።
(465) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 218። ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው ገጽ 24-26።



ሳይተክሏት በቅላ፣ ውኃ ሳያጠጧት አብባ ለውዝ፣ ገውዝ፣ በኵረ ሎሚ አፍርታ የተገኘች በትረ አሮን አንቺ ነሽ»(466) በማለት ያመሰግናታል። ሊቁ አባ ጊዮርጊስም «በትረ አሮን ማርያም ዘሠረጽኪ እንበለ ተክል ወጸገይኪ ጽጌ በኢተሰቅዮ ማይ ወጠል»(467) ሲል በአጽንኦት መስክሮአል። በዚህም ምክንያት ኦርቶዶክሳውያን ክርስቲያኖች እመቤታችንን፦

**«ልትገለብጠኝ የሔዋን መኪና፣**
**ማርያም አዳነችኝ ፍሬን ያዘችና።»**

በማለት በኅቱም ድንግልና ያስገኘችው ፍሬ ሕይወት ጌታ ድኅነተ ሥጋ፣ ድኅነተ ነፍስን የሚሰጥ የሕይወት ባለቤት መሆኑን ዘወትር ይመሰክራሉ።

ዳግመኛም አበው «የእናት ልመና ፊት አያስመልስ፣ አንገት አያስቀልስ» እንዲሉ ሊቁ ቅዱስ አባ ሕርያቆስ በቅዳሴው የቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያምን የአማላጅነቷን ቃል ኪዳን አስመልክቶ ሲናገር «በኀበ ኵሉ ዘተሰምየ መካነ ሰማዕት መዋዕያን ወመካነ ጻድቃን ቡሩካን። ወመካነ መላእክት ትጉሃን በኀበ ኵሉ መካን ርእስተ አንቲ። ወሥሉጥ ስምኪ በኀበ እግዚአብሔ ር»(468)፤ ዓላውያን ነገሥታት፣ ዓላውያን መኳንንትን፣ ፍትወታት እኩያት ኃጣውእን ድል የነሡ ሰማዕታት ስማቸው በተጠራበት ሁሉ፤ እናንተ የአባቴ ቡሩካን ወደ እኔ ኑ የተባሉ ጻድቃን ባሉበት ሁሉ፤ እንዲሁም ምስጋናቸው ዕረፍታቸው፣ ዕረፍታቸው ምስጋናቸው ሆኖላቸው ዘወትር በማያቋርጥ ውዳሴ፣ ቅዳሴ ጸንተው ምስጋናን የሚያቀርቡ ሰማያውያን ቅዱሳን መላእክት ባሉበት ሁሉ፣ በቦታው ሁሉ አንቺ ርስት ነሽ። ስምሽም በልዑል እግዚአብሔር ዘንድ ለማማለድ ሥልጡን ነው በማለት መስክሯል።

(466) ቅዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 93-94።
(467) አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ፣ መጽሐፈ ሰዓታት፣ ገጽ 597።
(468) መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 223-225። ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 48-55። ቅዱስ ያሬድ፣ «አንቀጸ ብርሃን»፣ ገጽ 409-410።

ይህንን አማናዊ የአማላጅነት ጸጋዋንና ክብሯን በመግለጥ ኢትዮጵያዊው ሊቅ አባ ጽጌ ድንግል ሲያመሰግናት፡- «ማርያም ለጴጥሮስ ጽላሎቱ ወለጳውሎስ ለበኑ። ብኪ ምውታን ሕያዋን ኮኑ፤ ድንግል ማርያም ሆይ ሊቀ ሐዋርያት ቅዱስ ጴጥሮስ በጽላሎተ ርእሱ(በጥላው)፣ ቅዱስ ጳውሎስ ደግሞ በዘፈረ ልብሱ (በልብሱ ዘርፍ) ድውያንን የፈወሱብሽና ገቢረ ተአምራት ወመንክራት ያደረጉብሽ ረድኤታቸውና ሞገሳቸው አንቺ ነሽ።»[469] ሲል በአጽንኦት መስክሮአል። (የሐዋ. ሥራ 5÷15-16፤ 19÷11-12፤ ኢሳ. 6÷1፤ ማር. 5÷25-34)

በመጨረሻም ዘወትር በቅዳሴ ጊዜ ሠርሆተ ሕዝብ ከመደረጉ አስቀድሞ ንፍቁ ካህን የክርስቶስ ምሥጢራዊ አካል ለሆኑት ማኅበረ ቤተ ክርስቲያን ከዚህ የሚከተለውን ጸሎት ይጸልያል፡- «ወዕቀበሙ በርትዕት ሃይማኖት በስብሐት ወክብር በኵሉ መዋዕለ ሕይወቶሙ። ወረስዮሙ ውስተ ፍቅረ ሰላም እንተ ትትሌዓል እምኵሉ ልቡና። በስእለት ወበእስተብቍዓት እንተ ትገብር በእንቲአነ እግዝእተ ኵልነ ወላዲተ አምላክ ቅድስት ወንጽሕት ማርያም።»[470] ይህም ማለት አምላክን የወለደች ቅድስት ድንግል እመቤታችን ማርያም በምትለምነው ልመና፣ በእርሷ አማላጅነት ባለ ዘመናቸው ሁሉ በክብር ለመኖር በቀናች ሃይማኖት ጠብቃቸው። ከሁሉ በምትበልጥና ልቡናም መርምሮ በማያገኛት ፍቅር አኑራቸው፣ አጽናቸው (1ኛ ቆሮ. 13÷1-3) ማለት ነው።

በአጠቃላይ በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ክብረ ቅድስት ድንግል ማርያም ከነገረ ድኅነት ጋር ያለውን ምሥጢራዊ ትምህርት አስመልክቶ ከላይ በዝርዝር የተመለከትናቸው የዐሥራው መጻሕፍት ምስክርነትና የመጻሕፍተ ቅዳሴያት አስተምህሮ ኦርቶዶክሳዊ ነገረ ማርያም የነገረ ድኅነት ምንጭና መሠረት መሆኑን በስፋት የሚገልጹና በአጽንኦት የሚመሰክሩም ናቸው።

---

(469) አባ ጽጌ ድንግል፣ «ማኅሌተ ጽጌ»፣ ገጽ 622።
(470) *መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ገጽ 152።*



# የክለሳ ጥያቄዎች

1. በኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያናችን ወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም ያላትን ልዩ የክብር ሥፍራ ይግለጹ።
2. በታቦተ ጽዮንና በአማናዊቷ ታቦት በድንግል ማርያም መካከል ያለውን ምሥጢራዊ ንጽጽር ያብራሩ።
3. በወንጌለ ቅዱስ ሉቃስ 1÷26-45፤ 11÷27 ላይ የተጠቀሱት ቃላተ ውዳሴያት «የወንጌል ውዳሴ ማርያም»፣ «የወንጌል መልክዐ ማርያም» መባላቸው ስለ ምንድን ነው?
4. የእመቤታችን የድንግል ማርያም አማላጅነት የቅዱሳን ሁሉ ጸሎትና ምልጃ አክሊል (ጉልላት) ነው ባልነው መሠረት የቤዛዊተ ዓለም ድንግል ማርያምን አማላጅነት አብራርተው ይግለጹ።
5. በኦርቶዶክሳውያን የቅዱሳት ሥዕላት ሊቃውንት ዘንድ «መራሒተ ፍኖት» በመባል የሚታወቀው የእመቤታችን ሥዕል ክብረ ቅድስት ድንግል ማርያምን ከነገረ ድኅነት ጋር በማገናዘብ የሚገልጸው እንዴት ነው?
6. «አንቺ ሴት ከአንቺ ጋር ምን አለኝ? ጊዜዬ ገና አልደረሰም» የሚለውን የዮሐንስ ወንጌል 2÷4 ኃይለ ቃል አብራርተው ያስረዱ።
7. መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የመጀመሪያውን አምላካዊ ተአምር በእናቱ በድንግል ማርያም አማላጅነት በገሊላ ቃና ሠርግ ቤት ያደረገው ስለምንድን ነው?
8. የወላዲተ አምላክ ድንግል ማርያም ዕረፍትና ፍልሰት (ዕርገት) ከነገረ ድኅነት ጋር ያለውን ምሥጢራዊ ግንኙነት ይግለጹ።
9. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን መጻሕፍተ ቅዳሴያት ክብረ ቅድስት ድንግል ማርያምን አስመልክቶ ያላቸው አስተምህሮ ምንድን ነው?